# ምዕራፍ ፲፫

## በጄኔቭ የንጉሠ ነገሥቱ አቤቱታ የፍርድ ያለህ !

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለአምሳ ሁለት መንግሥታት እንደራሴዎች ንግግራቸውን የጀመሩት፤ " ... የዓለምን ሰላምና የአገሮችን ነጻነት ለማስከበር ከፍተኛ የቃል ኪዳን አደራ የተጣለበት የመንግሥታት ማህበር፤ የአንድ አባል አገር መሪ የሆነ ንጉሠ ነገሥት ሌላው አባል መንግሥት በጦር ኃይል ተደራጅቶ በሕዝቡ ላይ ስለአደረሰበት አሠቃቂ የሆነ እልቂት፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ሸንጎ ላይ ተገኝቶ አቤቱታውን የሚያቀርበው ለመጀመሪያ ጊዜ መሆኑን የሚስተው ይኖራል ብዬ አላስብም ... " በሚል ቃል ነበር።

ከብዙ ሺህ ዓመታት ጀምሮ ነጻነቱን ጠብቆ የኖረውን የአገሬን የኢትዮጵያን ሕዝብ፤ በአሁኑ ሰዓት የጣልያን መንግሥት ቅኝው አድርጎ ለመግዛት በጦር ኃይልና በመርዝ ጋዝ የሚፈጽምበት ግፍና ጭካኔ፤ ከዚህ ቀደም በሠለጠነው ዓለም ውስጥ ደርሶ ያልታየና ተወዳዳሪ የማይገኝለት መሆኑን የምገልጽላችሁ እጅግ በመረረ የኃዘን ስሜት ነው።

የጣልያን መንግሥት፤ ካለፈው አንድ ዓመት ተኩል ጀምሮ በአገሬ በኢትዮጵያና በሕዝቤ ላይ ሲወስድ የቆየው ሕገ ወጥ እርምጃ፤ ምን ያህል አሳሳቢና ምን ያህል አደገኛ እንደሆነ፤ በየጊዜው ለመንግሥታት ማህበር ያመለከትኩባቸው ሰነዶች፤ በጽሕፈት ቤቱ ተመዝግበው የሚገኙ መሆናቸውን ማስታወስ እፈልጋለሁ። ሆኖም፤ በዛሬው ዕለት የአምሳ ሁለት መንግሥታት እንደራሴዎች፤ የኢትዮጵያን አቤቱታ ሰምታችሁ ፍርዳችሁን ለመስጠት ስለተሰበሰባችሁ፤ የወልወል ግጭት ከተፈጠረበት ጊዜ አንሥቶ እስከዛሬ ድረስ፤ የጣልያን መንግሥት በአገሬና በሕዝቤ ላይ የፈጸማቸውን ግፍና በደል ዋና ዋናዎቹን ልገልጽላችሁ ከፊታችሁ ቀርቤያለሁ።

1ኛ/ እ.ኤ.አ ታኅሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም በደቡብ ኢትዮጵያ በሚገኘው **"ወልወል"** በተባለው ግዛታችን ውስጥ የጣልያን ሱማሌ ወታደሮች ገብተው በፈጠሩት ግጭት፤ አንድ መቶ ሰባት ኢትዮጵያውያኖችን ገድለው፤ ዐርባ አምስት የሆኑትን አቆሰሉ። በዚህ ጊዜ የደረሰውን አሳዛኝ ሁኔታ ኢትዮጵያ ለመንግሥታት ማህበር ወዲያውኑ ስታመለክት፤ የሮማ መንግሥት ደግሞ በበኩሉ ኢትዮጵያ የግዛቱን ወሰን ጥሳ በፀጥታ አስከባሪ ወታደሮቼ ላይ አደጋ ጥላብኛለች የሚል የፈጠራ ክስ አቀረበ። ጉዳዩ በሰላማዊ መንገድ እንዲያልቅ በማሰብ፤ በሁለቱ አገሮቻችን መካከል በ1928 ዓ.ም በተፈረመው የወዳጅነት ስምምነት መሠረት፤ ከሁለቱም መንግሥታት በኩል ሽማግሌዎች ተመርጠው አጥፊው ማን መሆኑን እንዲለዩ ኢትዮጵያ ስትጠይቅ፤ የመንግሥታት ማህበርም ሐሳቡን በደስታ መቀበሉን አስታወቀ። ነገር ግን፤ የጣልያን መንግሥት



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በመንግሥታት ማህበር ሸንጎ ላይ፤ የፍርድ ያለህ!

ዓላማውና ግቡ የተለየ ስለሆነ፤ 1ኛ/ በጋራው ስምምነታችን መሠረት፤ የሚመረጡት ዳኞች የማንም ወገን ያልሆኑ ከልዩ ልዩ አገሮች የተውጣጡ ሰዎች መሆናቸው ቀርቶ፤ በጣልያን በኩል የኮሎኒዎቹ አስተዳደር ሚኒስቴር ባለሥልጣኖች የሆኑትን በማድረግ፤ 2ኛ/ የተመረጡት ሽማግሌዎች የሚያጠኑት፤ "ወልወል" ላይ የደረሰው አደጋ በማን ጥፋት መሆኑን እንጂ፤ "ወልወል" የማን ግዛት እንደሆነ፤ መርምሮ የመለየት ኃላፊነት አይሰጣቸውም ሲል፤ አስገራሚ የሆነ የዕብሪት ሐሳብ አቀረበ። የሮማ መንግሥት ይህንን ችግር ለመፍጠር የፈለገው፤ "ወልወል" የተባለው ቦታ ከጣልያን ሱማሌ ወሰን በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ አንድ መቶ ኪሎ ሜትር ርቆ የሚገኝ ስለሆነ፤ ሽማግሌዎቹ በቀላሉ የሚደርሱበት መሆኑን በመፍራት ነበር። ኢትዮጵያ ግን፤ "ባንዳ " የተባሉት የጣልያን ሱማሌ ወታደሮች፤ "ወልወል" በተባለው ግዛቷ ላይ፤ ወሰን ጥሰው በመግባት ስለአደረሱባት አደጋ፤ ማስረጃዋን በዝርዝር አዘጋጅታ ለተመረጡት ሽማግሌዎችና ለመንግሥታት ማህበር በማቅረብ፤ ትክክለኛ የሆነ አቋሟን አሳይታ ተፈርዶላታል።

2ኛ/ የወልወል ግጭት ከደረሰበት ከታኅሣሥ 1934 ዓ.ም ጀምሮ፤ በኢትዮጵያ ሰሜንና ደቡብ በኤርትራና በሱማሌ በኩል፤ የጣልያን መንግሥት ከፍ ያለ የጦር ዝግጅት ማድረጉን ቀጠለ። ይህም በሁለት ግንባር የሚደረገው ዝግጅት፤ ኢትዮጵያን ለመውረር መሆኑን የሮማው መንግሥት መሪ ለመላው የጣልያን ሕዝብ በይፋ ስለገለጸው፤ የመንግሥታት ማህበር በተቋቋመበት ዓላማ መሠረት፤ መርማሪ ኮሚሽን ወደ ሥፍራው ልኮ እንዲያጣራና እርምጃ እንዲወስድበት ኢትዮጵያ ደጋግማ ማመልከቷን አላቋረጠችም ነበር። የጣልያን መንግሥት ደግሞ በበኩሉ፤ ኢትዮጵያ በቅኝ የያዝኳቸውን የኤርትራንና የሱማሌ ግዛቶቼን ለመቀማት በወሰኖቻችን ላይ ጦር ስለአሰፈረች፤ ጣልያንም መከላከያዋን በማዘጋጀት ላይ ትገኛለች ሲል፤ የተለመደ የቅጥፈት መልሱን ለሊግ ኦፍ ኔሽን አቀረበ። በዚህ ጊዜ የመንግሥታት ማህበር፤ ኢትዮጵያ ደጋግማ እንዳመለከተችው፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ ወሰኖች ላይ መርማሪ ኮሚሽን ልኮ ጦር በማዘጋጀት ላይ የሚገኘው የማን መንግሥት እንደሆነ በማጣራት ፋንታ፤ ቀደም ሲል በሁለቱ አገሮች መካከል ስለተፈጠረው ችግር፤ እስታራቂ መፍትሔ እንዲፈልግ የተቋቋመው የአሥራ ሦስቱ አባላት ኮሚቴ ይህንንም የጦሩን ዝግጅት እንዲመረምር አስተላለፈ። ይህም ዓይነቱ ውሳኔ፤ ለጣልያን መንግሥት ሰፋ ያለ ጊዜ የሰጠው ስለሆነ፤ በኤርትራና በሱማሌ በኩል ያቀደውን ከፍተኛ የጦር ዝግጅት በሚገባ ካጠናቀቀ በኋላ፤ እ.ኤ.አ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም የፋሽስት የአየር ኃይልና የምድር ጦር ወሰናችንን ጥሰው ወረራውን ጀመሩ። ወዲያውም ኢትዮጵያ ከሕግ ውጭ የደረሰባትን ጥቃት ለመንግሥታት ማህበር አቤት ስትል፤ ጦርነቱን የጀመረው ጥፋተኛ ማን መሆኑን ለማወቅ ስድስት የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች የተሠየሙበት ልዩ ኮሚቴ እንዲቋቋም ተደረገ። በመሠረቱ፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ጦርነት አዘጋጅውና አጥቂው ማን መሆኑን ለማወቅ የተለየ ምርምር የሚያስፈልገው አልነበረም። የመንግሥቱ ጠቅላይ ሚኒስትር ሲኞር ሙሶሊኒ ራሱ ለመላው የጣልያን ሕዝብ ባደረገው ንግግር፤ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም ከብዙ ጊዜ ጀምሮ ሲሰናዳ የቆየው የፋሽስት ጦር ኃይል፤ የኢትዮጵያን ወሰን ጥሶ "አድዋን" መያዙንና ቀጥሎም መላ ኢትዮጵያን

ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ፤ ሠራዊቱ ወደፊት እየገፋ ውጊያውን የቀጠለ መሆኑን በይፋ ስለአስታወቀ፤ የመንግሥታት ማህበር ከዚህ የበለጠ መረጃ ያስፈልገዋል ብለን አላሰብንም ነበር። ሆኖም፤ ጦርነቱን በመጀመር ጥፋተኛው ማን መሆኑን አጣርቶ እንዲያቀርብ የታዘዘው ይህ የስድስቱ አባላት ኮሚቴ፤ የጣልያንን መንግሥት ሕገ ወጥነት አረጋግጦ ለማቅረብ ከሁለት ቀናት የበለጠ ጊዜ አልወሰደበትም። እንደዚሁም፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረውን ጠብ ከመነሻው ጀምሮ በማጥናት አስተያየቱን እንዲሰጥ የተቋቋመው የአሥራ ሦስት አባላት ኮሚቴ ባደረገው ምርምር፤ ከወልወል ግጭት አንሥቶ በተካሄዱት ጉዳዮች፤ ኢትዮጵያ ሰላም ፈላጊነቷን ከማሳየት በስተቀር፤ ምንም ዓይነት ጥፋት እንዳልተገኘባትና፤ ይልቁንም ከሊግ ኦፍ ኔሽን የሚሰጠውን ውሳኔ ሁሉ በትክክል የፈጸመች መሆኗን ለመንግሥታት ማህበር ከማረጋገጥ አልተቆጠበም።

3ኛ/ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም፤ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነት የከፈተው የጣልያን መንግሥት መሆኑ ከተረጋገጠ በኋላ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን መተዳደሪያ በአንቀጽ 16 መሠረት አጥፊውን በኤኮኖሚ ዕገዳ ለመቅጣት፤ አስፈላጊውን ዝርዝር አጥንቶ የሚያቀርብ አሥራ ስምንት (18) አባል አገሮች የተሠየሙበት ኮሚቴ መቋቋሙ ተገለጸ። ይህም ኮሚቴ ከአሥር ጊዜ የበለጠ ስብሰባ በማድረግ ካጠና በኋላ፤ የሚወሰዱት የኤኮኖሚ ዕገዳዎች ምንና ምን መሆናቸውን ዘርዝሮ ሲያቀርብ፤ በሕገ ወጡ መንግሥት ላይ ከባድ ጉዳት ሊያደርሱና፤ ጦርነቱንም እንዲያቆም ሊያስገድዱት የሚችሉትን እንደ ነዳጅ ዘይት፤ ከሰልና ብረታ ብረት የመሳሰሉትን ዋና ዋና ጉዳዮች በሊስቱ ውስጥ ሳይጨምራቸው ቀረ። እነዚህ እጅግ አስፈላጊዎችና መሠረታዊ የሆኑት ነገሮች ካልታገዱበት፤ ሕገ ወጡ መንግሥት ምን ጉዳት ደርሶበት የኢትዮጵያን ሕዝብ ለመጨረስ የሚያነደውን የጦርነት እሳት እንዲያቆም ይገደዳል? .... በማለት፤ በዠኔቭ የሚገኘው መልዕክተኛዬ የእንግሊዝንና የካናዳን ድጋፍ አግኝቶ ቢከራከርም የሚያዳምጠው ሳያገኝ ቀረ። ይህም ሁኔታ፤ ምንም እንኳ ከአምሳ ሁለቱ የመንግሥታት ማህበር አባሎች መካከል፤ ከሁለትና ከሦስት አገሮች በስተቀር፤ ሁሉም በአንድነት የጣልያንን ሕገ ወጥነት ተገንዝበው በማውገዝ ድምፃቸውን የሰጡ ናቸው ቢባልም፤ በኤኮኖሚ እገዳ ረገድ በሚደረገው ውሳኔ የፋሽስቱ መንግሥት ጉዳት ላይ ወድቆ የሚያካሂደውን ጦርነት ለማቆም እንዲገደድ ሁሉም የሚፈልጉ እንዳልነበሩ የሚያሳይ ሆኗል።

ኮሚቴ አሥራ ስምንት፤ ስለ ኤኮኖሚው ዕገዳ ጉዳይ በሚነጋገርበት ጊዜ፤ ምናልባት እንደ ነዳጅ ዘይት የመሳሰሉትን ሁሉ የሚጨምር ከሆነ፤ በመንግሥቴ ላይ ከባድ ችግር ያደርስብኛል ብሎ በመሥጋት፤ የፋሽስቱ መሪ ከኢትዮጵያ ጋር የሰላም ንግግር ለመጀመር እንደሚፈልግ በልዩ ጉዳና እኛ እንድናውቀው አድርጎ ነበር። ነገር ግን፤ በኮሚቴ አሥራ ስምንት አሳሳቢነት በመንግሥታት ማህበር በኩል የተወሰነው የኤኮኖሚ ዕገዳ፤ ጣልያንን ችግር ላይ እንደማይጥላት ሲያውቅ፤ የፋሽስቱ መሪ ሲኞር ሙሶሊኒ ጦርነቱን በመቀጠል መላ ኢትዮጵያን ከመያዝ በስተቀር፤ የሰላም ንግግር መክፈት አስፈላጊ አይደለም ብሎ ወሰነ። ጦርነቱንም አፋጥኖ ከሚፈልገው ግብ ለመድረስ ሲሞክር፤ የኢትዮጵያ ሠራዊት የሚያደርገው መከላከል ስለጠነከረበት፤ የፋሽስቱ ጦር አዛዥ እ.ኤ.አ ከታህሣሥ 22 ቀን 1935

ዓ.ም ጀምሮ ለአራት ወራት ባለማቋረጥ የውጊያውን አመራር ለውጦ፣ በዓለም ሕግ የተከለከለውን ኢፔሪት የተባለውን ፈሳሽ የሆነ የጋዝ መርዝ በአውሮፕላን እየረጨ ማጥቃት ጀመረ። ይህንን ፈሳሽ መርዝ የሚጥሉት አውሮፕላኖች፣ በዘጠኝ፣ በአሥራ አምስትና በአሥራ ስምንት መንታ እየተከፋፈሉ፣ ከሰማይ እንደ ካፊያ ዝናብ የሚረጩት በጦሩ ሜዳ ላይ በሚዋጋው ሠራዊት ላይ ብቻ ሳይሆን፣ በየቤተ ክርስቲያኑና በየገበያው በሚሰበሰበው ሰላማዊው ሕዝብ ላይ ስለሆነ፣ በጋዙ መርዝ እየነደዱ ያለቁት ወንዶችና ሴቶች፣ ልጆችና ሕፃናቶች ቁጥራቸው ምን ያህል እንደደረሰ በዛሬው ሰዓት ሊታወቅ አልቻለም። ከዚህም በቀር የተረጨው መርዝ በወንዞችና በኩሬዎች፣ በእህል ማከማቻ ጉተራዎችና በከብት ማሠማሪያዎች ላይ ስለሆነ፣ ውሃ የሚጠጣውንም ሆነ ምግብ ሠርቶ የሚቀምሰውን ሕዝብ፣ ወዲያውኑ እያሰቃየ ገድሎታል። ከብቱም በዚሁ አኳኋን አልቋል። ይህንን ከዚህ ቀደም በዓለም ሕዝብ ላይ ደርሶ የማይታወቀውን በሰው ልጅ ላይ የሚደረገውን አሰቃቂ የሆነ የጭካኔ ሥራ፣ እኔ ራሴ በጦሩ ሜዳ ላይ ተገኝቼ በተዋጋሁበት ሰዓት፣ ዛሬ እዚህ መልዕክተኞቼ ሆነው ከመጡት የጦር አለቆች ጋር አብረን በዐይናችን ያየነው ስለሆነ፣ ከእኛ የተሻለ ለመንግሥታት ማህበር ምስክርነት ለመስጠት የሚችል ይገኛል አንልም።

እንግዲህ ! እዚህ ለተሰበሰባችሁት የመንግሥታት እንደራሴዎች ግልጽ ሆኖ እንደሚታያችሁ፣ በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ ለሚፈጸመው ተወዳዳሪ ለሌለው የግፍና የጭካኔ ሥራ፣ በአጥቂውና በሕገ ወጡ መንግሥት ላይ በሊግ ኦፍ ኔሽን አንቀጽ 16 መሠረት የተወሰደው እርምጃ፣ በቂ ነበር ወይ ? ብሎ መጠየቅ ያስፈልጋል። እኛ ተጠቂዎቹ እንደተረዳነውና አንዳንዶቹም አባል አገሮች እንደ ታዘቡት፣ የተደረገው የኤኮኖሚ ዕገዳ እጅግ ደካማ በመሆኑ፣ የአጥቂውን መንግሥት ጉልበትና ጭካኔ ሊቀንሰው አልቻለም። ከዚህም በቀር በጣም አሳዛኝ ሆኖ የሚታየው፣ እነዚህን ደካማዎቹን የኤኮኖሚ ዕገዳዎች፣ ብዙዎቹ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባላት፣ የፋሽስቱን መንግሥት በመደገፍ በትክክል ሳይፈጽሙት መቅረታቸው ነው። ለዚህም የምናቀርበው አንድ ምሳሌ ብቻ በቂ መሆን ይችላል። ጥቅምት 18 ቀን 1935 ዓ.ም ስለ ኤኮኖሚ ዕገዳዎች ጉዳይ በተደረጉት ውሳኔዎች ውስጥ፣ ወደ ኢትዮጵያ የሚላኩት የጦር መሣሪያዎች ምንም ዓይነት ቁጥጥር ሳይደረግባቸው በነፃ መግባት እንደሚችሉ ተገልጾ ነበር። እኛም፣ ገና ከጦርነቱ በፊት ለአገር ፀጥታ መጠባበቂያ እንዲሆኑን፣ ታላላቆቹ መንግሥታት ፈቅደው የገዛናቸው መሣሪያዎች ጂቡቲ ሲደርሱ ተይዘውብን ስለነበረ፣ በዚህ በአዲሱ ውሳኔ መሠረት በአስቸኳይ እንዲለቀቁልን አመለከትን። በጂቡቲ የሚገኙት የፈረንሣይ መንግሥት ባለሥልጣኖች፣ ፈቃዱ ከፓሪስ እስኪደርሰን በመጠባበቅ ላይ ነን የሚል ምክንያት እየሰጡ አለአግባብ ካዘገዩት በኋላ፣ የጣልያን ጦር እየገፋ ወደ አዲስ አበባ ሲቃረብ በባቡር አሳፍረው በመላክ፣ ድሬዳዋ ላይ የፋሽስት ወታደሮች ጠብቀው እንዲረከቡት አስደረጉ። ይህም በኢትዮጵያ ላይ የተፈጸመው የግፍ አሠራር፣ ያለጥርጥር በጥር 7 ቀን 1935 ዓ.ም ሮም ላይ በጣልያንና በፈረንሣይ የፖለቲካ መሪዎች መካከል በተፈረመው የምሥጢር ስምምነት መሠረት ነው ቢባል፣ ሀሰት ነው የሚል ይኖራል ብለን አናስብም።

የተከበራችሁ የመንግሥታት እንደራሴዎች፣

ቀደም ብዬ እንደ ተናገርኩት፣ የዛሬ አሥራ ሰባት ዓመት የተመሠረተው የመንግሥታት ማህበር ዋና ዓላማውና ግብሩ፣ ኃይለኛው መንግሥት አቅሙን ተማምኖ ደካማውን እንዳያጠቃ፣ ትክክለኛውን ፍርድ ለመስጠትና የትልቁን ሆነ

የትንሹን መብት በእኩል ደረጃ ለማስከበር ስለሆነ፤ አንድ አባል መንግሥት በዕብሪት ተነሥቶ በሌላው አባል አገር ላይ የሚፈጽመውን ግፍ ዘርዝሬ በማቅረብ ፍርዳችሁን ጠይቂያለሁ። ለዚህም፤ ትክክለኛ ፍርድ እንድትሰጡኝ ያቀረብኩላችሁ ጥያቄዎች፤ በሚከተሉት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ተመሥርቼ መሆኑን እንድታውቁልኝ እፈልጋለሁ።

-- የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆነችውን ኢትዮጵያን ነጻነቷን ገፍፎ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ፤ የጣልያን መንግሥት የወሰደው የጦርነት እርምጃ የመንግሥታት ማህበርን ሕግ በመጣስ መሆኑን፤ ሙሉ በሙሉ አታምኑበት ይሆን ?

-- ሕገ ወጡ መንግሥት በከፈተው ጦርነት በቶሎ ማሸነፍ ሲያቅተው፤ የዓለም መንግሥታት የከለከሉትንና የጣልያን መንግሥት ራሱ ተስማምቶ ዤኔቭ ላይ የፈረመውን ሕግ ጥሶ፤ የኢፐሪት ፈሳሽ የጋዝ መርዝ በአውሮፕላን እያዘነበ፤ የኢትዮጵያን ሕዝብ መጨረሱ ከወንጀል በላይ ወንጀል መሆኑን ተገንዝባችሁት ይሆን ?

-- አንድ አባል አገር ይህንን የመሰለ የጭካኔ ግፍ ሲፈጸምበት፤ በሕገ ወጡ መንግሥት ላይ ሊግ ኦፍ ኔሽን የወሰነው የኢኮኖሚ ዕገዳ ቅጣት በቂ ነው ለማለት ትደፍሩ ይሆን ?

-- እነዚህ ደካሞቹ የኢኮኖሚ ዕገዳዎች፤ በግፈኛው መንግሥት ላይ የሚያደርሱት ከባድ ጉዳት አለመኖሩ ቢታወቅም፤ በውሳኔው መሠረት ብዙዎቹ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች ሳይፈጽሙት መቅረታቸው፤ እጅግ የሚያሳዝን መሆኑ አይሰማችሁ ይሆን ?

-- በመንግሥታት ማህበር ደንብና ሕግ ላይ ዕምነቷን በመጣል፤ ሰላምን አጥብቃ የምትፈልግና ሕዝቧን ከጨለማው ዓለም ለማላቀቅ የምትጥር ኢትዮጵያ፤ ነፃነቷ ሲገፈፍና ልጆቿ በመርዝ ጋዝ ሲቃጠሉ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን ይችን ድሃ አገር ለማዳን ምን እርምጃ መውሰድ እንደሚገባው፤ ዛሬ ማሰብና መቁረጥ ካልቻላችሁ፤ ነገ ጊዜው የናንተ እንደማይሆን ተገንዝባችሁት ይሆን ?

-- በሊግ ኦፍ ኔሽን ደንብ መሠረት፤ አንድ አባል መንግሥት ሌላውን አባል አገር በጦር ኃይል ሲወጋው ከተገኘ፤ ጥቃቱ በመላው አባል አገሮች ላይ እንደ ተፈጸመ ተቆጥሮ፤ በሕገ ወጡ ላይ የሁሉንም ትብብር ያቀፈ እርምጃ ይወሰድበታል የተባለውን፤ ዛሬ ለኢትዮጵያ እንዲውል ካላደረጋችሁ፤ ወደፊት ለየትኞቹ አገሮች ሊሠራ እንደሚችል የወሰናችሁት ነገር ይኖር ይሆን ? ....

የመንግሥታት እንደራሴዎች ሆይ !

በዛሬው ሰዓት ኢትዮጵያን በጦር ኃይል በመውረር የአገሩን ሕዝብ በመጨረስ ላይ የሚገኘው የጣልያን መንግሥት፤ የዓለምን ሕግጋት በመጣስና የኢንተርናሽናል ስምምነቶችን በማፍረስ ተወዳዳሪ የሌለው ሕገወጥ መሆኑ መታወቅ አለበት። ለምሳሌም ያህል ከብዙዎቹ ጥቂቶቹ:-

1. የጣልያን መንግሥት ራሱ መሥራች አባል ሆኖ የዛሬ አሥራ ሰባት ዓመት የተቋቋመውን ይህንን የመንግሥታት ማህበር፤ ደንቡንና ሥርዓቱን ጥሶ

አባል የሆነችውን ኢትዮጵያን ነጻነቷን በመግፈፍ በወሰደው እርምጃ፣ ጠላትነቱ የአምሳዎቹ አባል አገሮች ጭምር እንዲሆን የፈጸመው የመጀመሪያው ትልቁ ሕገ ወጥ ተግባር ነው።

2. በዓለም መንግሥታት መካከል የሚፈጠረው አለመግባባት፣ በሰላማዊ መንገድ ብቻ እንዲያልቅና ጦርነት ጨርሶ እንዲቀር፣ በነሐሴ 2 ቀን 1928 ዓ.ም በብዙዎች አገሮች ስምምነት የተደረገበትን የብሪያንድንና የኬሎግን፣ (Pacte-Briand-Kellogg) ውል ለማክበር፣ የጣልያን መንግሥት ራሱ ፈርሞት የነበረውን ራሱ መልሶ አፍርሶታል።

3. እንደዚሁም በሙሶሊኒ መንግሥት ጠያቂነት፣ በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል ለሐያ ዓመታት ፀንቶ እንዲኖር ነሐሴ 28 ቀን 1928 ዓ.ም የፈረምነውንና በሊግ አፍ ኔሽን ያስመዘገብነውን የሰላም ውል፣ ያለአንዳች ምክንያት በራሱ ኃይል ብቻ ሰርዞታል።

4. ማንም መንግሥት ኃይሉን ተመርኩዞ የሌላውን አገር መቀማት እንዳይችል፣ በ1933 ዓ.ም የደቡብ አሜሪካ አገሮች በሕብረት ያዘጋጁትን ውል፣ የጣልያን መንግሥት ከሌሎቹ የአውሮፓ አገሮች ጋር ተስማምቶ የፈረመ ሲሆን፣ ይህንንም ዛሬ በኢትዮጵያ ላይ በፈጸመው ሕገ ወጥ ሥራ ያፈረሰው መሆኑን አሳይቷል።

እነዚህን ሁሉ ለምሳሌ ያህል ብንጠቅሳቸውም፣ ዛሬ በአለንበት ሰዓት ከሁሉ ይበልጥ የዓለምን ሕዝብ እጅግ ሊያስጨንቀውና ሊያሳስበው የሚችለው፣ የዓለም መንግሥታት ተስማምተው ለሰላም የሚያወጧቸውን ሕጐች፣ በጉልበትና በማን አለብኝ መንፈስ እየተነሡ የሚደመስሱ መሪዎች መፈጠራቸው ነው። በዚህም አኳኋን፣ የፋሽስት መንግሥት ዛሬ በኢትዮጵያ ላይ የሚፈጽመውን የግፍ ሥራ ነገ በሌሎቹ አገሮች ላይ ለማድረግ ምን ያግደዋል ? ተብሎ የሚቀርበው ጥያቄ ነው። ለዚህም አስጨናቂ ጥያቄ፣ መልሱ ዛሬ ካልተገኘለትና አጥቂዎቹን ለመቋቋም ተገቢው እርምጃ ካልተወሰደ፣ አደጋው በድሆች አገሮች ላይ ብቻ ተወስኖ የሚቀር ሳይሆን፣ ታላላቆቹም መንግሥታት እንደሚደርስባቸው ሊያስቡበት ይገባል።

ከሥነ ፍጥረት ሕግና ከሰብዓዊ መንፈስ ውጭ፣ ያ ሁሉ አስቃቂ የሆነ ዕልቂት ቢደርስበትም፣ ሰላማዊና ሃይማኖተኛ የሆነው ያገሬ የኢትዮጵያ ሕዝብ፣ ለነጻነት የሚያደርገው ተጋድሎ እስከ ዕለተ ሞቱ የጠነከረ ስለሆነ፣ በየጫካው፣ በዱር በገደሉና በየበረሃው እየተዘዋወረ በመዋጋት፣ ጠላቱን ከማስጨነቅ አላቋረጠም። እኔም በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ጠላት ለመያዝ ሞክሮ ባቃተው በአንድ ልዩ ቦታ፣* አዲስ አበባ ያለውን የመንግሥቴን አስተዳደር ካዛወርኩ በኋላ፣ ወደ ዠኔቭ የመጣሁት፣ እውነትን ብቻ ተመርኩዤ አቤቱታዬን ለእናንተ ለማመልከትና፣ የመንግሥታት ማህበርን እርዳታ አግኝቼ፣ የነጻነት ትግሌን ወደምቀጥልበት ቦታ ለመሄድ መሆኑን እንድታውቁልኝ እፈልጋለሁ። ስለዚህም፣ በንግግሬ መደምደሚያ ላይ የምጠይቃችሁ፣ **ለሕዝቤ ምን ይዤለት እንደምመለስ መልሳችሁን እንድትሰጡኝ ነው።***

---

* ይህ ልዩ ቦታ የተባለው የይልባቦር ዋና ከተማ ጉሬ ነው።

* LEAGUE OF NATIONS OFFICAL RECORDS 30-06-36

# ምዕራፍ ፲፬

## ታሪካዊው የመንግሥታት ማህበር ዳኝነት

እንደ ኢት/አቆ ሐሙስ ሚያዝያ 22 ቀን 1928 ዓ.ም በምሽት፤ በአዲስ አበባ ቤተመንግሥት በተደረገው ስብሰባ ላይ፤ የንጉሠ ነገሥቱን ወደ ዤኔቭ ሄዶ ለሊግ ኦፍ ኔሽን አቤቱታ ማቅረብ እጅግ አስፈላጊነቱን የደገፉትና ያስወሰኑት ታላላቅ ሰዎች፤ በሁለት ዓይነት ዓላማና ግብ ላይ ተመሥርተው እንደነበረ ይታወሳል።

**ይኸውም:-**

**የመጀመሪያው**፤ ጃንሆይ ዤኔቭ ሄደው ለሊግ ኦፍ ኔሽን በሚያቀርቡት አቤቱታ፤ ኢትዮጵያን ከጠላቷ እጅ የሚያላቅቃት የጦር እርዳታ አግኝተው ወደ አገር ይመለሳሉ ብሎ ማለም ባይቻልም፤ ፋሽስት የዓለም መንግሥታት ያወጡትን ሕግ ጥሶ፤ በኢትዮጵያ ላይ የፈጸመውን ግፍ ዘርዝረው ሲያስረዱ፤ ያለጥርጥር ታላላቆቹ አገሮች አንድ ዓይነት እርምጃ ሳይወስዱ ዝም ብለው ሊመለከቱ አይችሉም። ከዚህ ሌላ ደግሞ፤ በአገራችን ሕዝብ ላይ የደረሰው እጅግ አሳዛኝ የሆነው በደል፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ሸንጎ ላይ በሚገባ ተገላልጦ ሲቀርብ፤ ያለ ጥርጥር የየመንግሥታቱ መሪዎች ለጥቅማቸው ሲሉ ጠላታችን የሆነውን ፋሽስትን በጦር ለመውጋት ባይፈልጉም፤ የየአገራቸው ሕዝብ ለኢትዮጵያ በማዘንና በመቆርቆር፤ ሰላማዊ ሰልፍ በማድረግም ሆነ በየጋዜጣው ላይ አስተያየት በመስጠት፤ ለነጻነታችን ለምናደርገው ትግል ጠቃሚ የሆኑ እርዳታዎችን ሊያስገኙልን ይችላሉ፤ የሚል ነበር።

**ሁለተኛው**፤ ጃንሆይ አገር ውስጥ ቆይተው በአርበኝነት ይታገሉ ቢባል፤ በማናቸውም ሁኔታ በጠላት ለመገደል የሚጠብቃቸው ዕድል ሰፊ ነው። የጃንሆይ መገደል ደግሞ፤ የኢትዮጵያን ነጻነት ተስፋ የሚያጨልምና የፋሽስትን የቅኝ አስተዳደር የማጠንከር ዕድል የሚሰጥ ይሆናል። ነገር ግን፤ ጃንሆይ ወደ አውሮፓ ተሻግረው ድምፃቸውን ለዓለም መንግሥታት እያሰሙ፤ የፖለቲካ ትግላቸውን ከቀጠሉ፤ በዱር በገደሉ ለሚዋጉት አርበኞቻችን ትልቅ ተስፋ ይሆናሉ። በተጨማሪም፤ በጀግኖቻችን ጥረት ጠላታችንም ሰላም እያጣ ብዙ ችግር ስለሚወድቅበት፤ አቅሙ እየተዳከመ ነጻነታችንን የማስመለስ ዕድላችን የተቃና ሊሆንልን ይችላል። ስለዚህ፤ ጃንሆይ በምንም ዓይነት አገር ውስጥ መቆየት የለባቸውም፤ ... የሚል ነው።

ንጉሠ ነገሥቱ ደግሞ በበኩላቸው፤ የቅርብ ረዳቶቻቸው ከሰጧቸው ምክር ጥቂት የተለየ አመለካከት ነበራቸው። በዤኔቭ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉባኤ ላይ ተገኝቶ አቤቱታ ማቅረብንና የዓለምን መንግሥታት ፍርድ መጠየቅ ተገቢ ይሆናል ብለው ቢያስቡም፤ **የመንግሥታት ማህበር የኢትዮጵያን ነጻነት ለማስመለስ የሚያደርገው ነገር ከሌለ፤ በአውሮፓ በስደት ሕይወት መቆየት አይታያቸውም ነበር። በኢትዮጵያ የሦስት ሺህ ዘመን ታሪክ ውስጥ፤ አንድ ንጉሠ ነገሥት የውጭ ጠላት ተነሥቶበት አገሩን ሲቀማው፤ ሕይወቱን ለማዳን ሕዝቡን ትቶ ወደ ስደት የሄደ ታይቶም ተሰምቶም ስለማይታወቅ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የመጀመሪያው ናቸው**

ተብለው፣ መተቸትንና በታሪክ መመዝገብን አልፈለጉም። ስለዚህም፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን ማህበርተኞች የሆኑት መንግሥታት ሁሉ፣ በተለይም ታላላቆቹ አገሮች፣ የኢትዮጵያን ነጻነት ለማስመለስ እርምጃ የማይወስዱ ከሆኑ፣ የንጉሠ ነገሥቱ በእነሱ አገር በስደት መቆየት፣ ለአገራችን ጥቅሙ ምንድን ነው ? የሚል አስተያየት ነበራቸው።

ይሁን እንጂ፣ ማናቸውም ሐሳብ ተሞክሮ ካልታየ፣ ውጤቱ ምን እንደሚሆን በቅድሚያ ሊታወቅ ስለማይችል፣ በመጀመሪያ ዤኔቭ ሄደው ለሚያቀርቡት አቤቱታ፣ ከመንግሥታት ማህበርና ከታላላቆቹም የኢትዮጵያ ወዳጆች ከሚባሉት አገሮች፣ ምን ዓይነት ፍርድ እንደሚያገኙ መጠበቅ ያስፈልጋል። በመጨረሻው፣ ከሊግ ኦፍ ኔሽን የሚገኝ እርዳታ ከሌለ፣ በአውሮፓ ቆይተው ከሚሠሩት የፖለቲካ ትግል፣ ወይም ደግሞ በአንዱ አመቺ በሆነ ጠረፍ በኩል ወደ አገር ተመልሰው ከሚያደርጉት የጫካ ውጊያ፣ የትኛው እንደሚቀልና የትኛው ውጤት እንደሚሰጥ ተነጋግሮ መወሰን ይሻላል በማለት፣ ዋና ዋናዎቹ አማካሪዎቻቸው የሰጧቸውን አስተያየት ንጉሠ ነገሥቱ ተቀብለው፣ የመጀመሪያው ሙከራ ወደሚደረግበት ወደ ዤኔቭ በመሄድ፣ ከዚህ በፊት በሚገኘው በምዕራፍ ፲፪ ላይ የተገለጸውን አቤቱታ ለአምሳ ሁለት መንግሥታት እንደራሴዎች አቀረቡ።

## ከንጉሠ ነገሥቱ ንግግር በኋላ የአባል አገሮች አስተያየት ምን ነበር ?

እ.ኤ.አ ሰኔ 30 ቀን 1936 ዓ.ም፣ (እንደ ኢት/አቆ ሰኔ 23/1928 ዓ.ም) የሰማዕቱ የቅዱስ ጊዮርጊስ በዓል በሚከበርበት ዕለት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በዤኔቭ ለአምሳ ሁለት መንግሥታት እንደራሴዎች አቤቱታቸውን ካቀረቡ በኋላ፣ የእያንዳንዱ አባል አገር አስተያየቱንና ውሳኔውን መስጠት የጀመረው፣ በማግሥቱ ከሐምሌ 1 ቀን ጀምሮ ነበር። በዚህ መሠረት፣ ጠቅላላው ጉባኤ ውሳኔውን እስከሰጠበት እስከ ሐምሌ 4 ቀን 1936 ዓ.ም ድረስ፣ በቀን ሁለት ጊዜ በተደረጉት ስብሰባዎች ላይ የሠላሳ አምስት መንግሥታት እንደራሴዎች በየተራ መድረኩ ላይ እየቀረቡ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን ምን ማድረግ እንደሚገባው ሐሳባቸውን ገልጸዋል። ከእነዚህ ከሠላሳ አምስቱ አገሮች መካከል፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን ዘንድ ተደማጭነት ያላቸው እንግሊዝና ፈረንሣይ አቋማቸው ምን እንደነበረ፣ እንዲሁም ከሶቪየት ሕብረት፣ ከሰሜን አውሮፓና ከላቲን አሜሪካ፣ ከአፍሪካና ከእስያ አንዳንድ አገሮች የሰጡት አስተያየት፣ ኢትዮጵያን ምን ያህል ረድቶ ወይም ምን ያህል ጎድቶ እንደሆነ ለመታዘብ፣ መመልከት ይጠቅማል።

## የታላቋ ብሪታንያ ንጉሣዊ መንግሥት ዋና መልዕክተኛ

የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን፣ የመጀመሪያው ተናጋሪ ሆኖ ከሊቀመንበሩ ጥሪው ሲቀርብለት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና መልዕክተኞቻቸው ብቻ ሳይሆኑ፣ የብዙዎች አገሮች እንደራሴዎች ጭምር፣ የታወቀው እንግሊዛዊው ፀረ ፋሽስት በሙሶሊኒ መንግሥት ላይ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን በጦር ኃይል እርምጃ ወስዶ የኢትዮጵያን ነጻነት ማስመለስ አለበት የሚል ትልቅ መግለጫ ይሰጣል ተብሎ ተጠብቆ ነበር። ነገር ግን፣ ከኤደን የተጠበቀውና የቀረበው አስተያየት እጅግ የተለያየ ሆኖ በመገኘቱ፣ እንኳንስ ፀረ ፋሽስቶቹን ቀርቶ፣ የፋሽስት ደጋፊዎች የሆኑትንም ጭምር ሳያስገርማቸው አልቀረም።

ንጉሠ ነገሥቱ ለአምሳ ሰባት መንግሥታት እንደራሴዎች ንግግራቸውን ሲጀምሩ፣ ባሮን አሎይዚ የሙሶሊኒ መልዕክተኛና የሊጉ ዋናው ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል ያዘጋጁቸው ባለጌዎቹ ፋሽስቶች በስብሰባው አዳራሽ ውስጥ ተሰግስገው፣ በፉጨት አዳራሹን በጥብጠውት ነበር። የሩማኒያው የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ኒኮላ ቲቱሌስኮ “እነዚህን አውሬዎች ለፍርድ ስትሉ አስወጡልን” ሲል በጋለ ንዴት ድምፁን አሰማ።



ኒኮላ ቲቱሌስኮ
የሩማኒያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር



ዮሴፍ አቬኖል፣
የሙሶሊኒ ደጋፊ የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና
ጸሐፊ (የፈረንሣይ ዜጋ)



ባሮን አሎይዚ፣
የሙሶሊኒ ዋና መልዕክተኛ

አንቶኒ ኤደን በንግግሩ መግቢያ ላይ፤ " ... የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት አገራቸው በግፍ ስለተወረረች፤ ዤኔቭ መጥተው በትናንትናው ዕለት ከፍ ያለ ክብር በተጐናጸፈው ስሜት ያቀረቡልን አቤቱታ፤ የሁላችንንም ልብ የነካ ነው። የደረሰው ሁኔታ አሳዛኝነቱ፤ ሥቃዩን ለሚቀበለው ለኢትዮጵያ ሕዝብ ብቻ ሳይሆን፤ እኛንም እጅግ አድርጎ የሚያስጨንቀን ነው ... " ካለ በኋላ፤ የታላቋ ብሪታኒያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ለጉባኤው በሁለት የሚከፈሉትን ዋና ዋና ሐሳቦች እንደሚከተለው አቀረበ።

1ኛ/ ባለፉት ሰባት ወራት በአጥቂው መንግሥት ላይ የተወሰነው የኢኮኖሚ ዕገዳ፤ በሚገባ በተግባር ላይ ሊውል ባለመቻሉና ውጤት ባለመስጠቱ፤ ሁላችንንም አሳዝኖናል። ነገር ግን፤ ዛሬ በምናየው የኢትዮጵያ ሁኔታ፤ ባለፈው የተወሰነው እንዲቀጥል፤ ወይም ሌላ ተጨማሪ የኢኮኖሚ ዕገዳ ይደረግ ቢባል፤ የተሻለ ውጤት ያመጣል ብሎ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት አያምንበትም። ኢትዮጵያን ከወራሪዋ ለማዳን የሚቻለው የጦር ኃይል እርምጃ ሲወሰድ ነበር። ይኸ ደግሞ አሁን ባለንበት ሰዓት በቶሎ የሚፈጸም ይሆናል ብሎ ማሰብ አይቻልም። ስለዚህ፤ በመንግሥታት ማህበር ደንብ አንቀጽ 16 መሠረት፤ በጣልያን መንግሥት ላይ የተወሰደው የኢኮኖሚ ዕገዳ፤ ጠቀሜታ ስለሌለው፤ ታላቋ ብሪታንያ እያዘነች ዕገዳው እንዲነሣ ትደግፋለች።

2ኛ/ በአጥቂው መንግሥት ላይ የተወሰነው ዕገዳ ይነሣ ቢባልም፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች በሙሉ በኢትዮጵያ ላይ ለጣልያን ይዞታ ዕውቅና እንዳይሰጡ ውሳኔ ማሳለፍ ያስፈልጋል ካለ በኋላ፤ አንቶኒ ኤደን ለንግግሩ መደምደሚያ ያደረገው፤ የአገሮችን ነጻነትና የሕዝቦችን መብት፤ አጥቂዎችንና ግፈኞችን ተቋቁሞ ለማስከበር የሚቻለው፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን የጦር ኃይል አቅም ሲያገኝ ስለሆነ፤ ምንም እንኳ ለዛሬው ችግራችን ሐሳቡን በግብር ለማዋል ባይመችም፤ ከዛሬ ጀምሮ ልናስብበትና ለማስፈጸም የምንችልበትን መንገድ መከተል አለብን፤ የሚል አስተያየት በመወርወር ነው።

የኢትዮጵያ ዋና ጠበቃ እየተባለ ዝናው የገነነለት አንቶኒ ኤደን፤ የቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴን እጅግ አሳዛኝ የሆነ አቤቱታ ካዳመጠ በኋላ፤ በፋሽስት መንግሥት ላይ የተፈረደው የኢኮኖሚና የፋይናንስ ጭቆና እንዲቆም ሐሳብ በማቅረብ፤ ከአምሳ ሁለቱ መንግሥታት መልዕክተኞች መካከል፤ የመጀመሪያው ይሆናል ተብሎ አልተጠበቀም ነበር። ገና ከጠዋቱ የወልወል ግጭት ከደረሰበት ጊዜ አንሥቶ፤ አንቶኒ ኤደን የፋሽስት መንግሥት ኢትዮጵያን ለማጥቃት የሚተበትበውን ተንኮል ሁሉ በጉባኤው ላይ እያጋለጠ ከማውገዝ ያላቋረጠ ሰው መሆኑ የሚታወስ ነው።

- በሰኔ ወር 1935 ዓ.ም አንቶኒ ኤደን ሮም ድረስ ሄዶ፤ ለሁለት ቀናት ከሙሶሊኒ ጋር ፊት ለፊት በመጋተር፤ የኢትዮጵያ ነጻነት ሳይነካ፤ በሁለቱ አገሮች መካከል ሰላምን ለመመሥረት ያደረገው ጥረት ቀላል አልነበረም።

- የፈረንሣይ መንግሥት ጠቅላይና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የነበረው ፒየር ላቫል፤ " ... የኢትዮጵያን ነጻነት ለማዳን ከመጣር፤ ከሙሶሊኒ ጋር ወዳጅነትን ማጠንከር ... " ለአውሮፓ ሰላም ዋስትና ይሰጣል እያለ ሊያግባባው ሲሞክር፤ አንቶኒ ኤደን እንኳንስ ሊተባበረው፤ ለማዳመጥ እንኳን አለመፈለጉ የሚካድ አይደለም።

- የፋሽስት ጦር ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም የኢትዮጵያን ወሰን ጥሶ ወረራውን በጀመረ ጊዜ፣ የሙሶሊኒ ወዳጆች እነ ፒየር ላቫልና እነ ዮሴፍ አቬኖል ጉዳዩ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ካውንስል ሳይቀርብ እንዲዘገይ፣ ብርቱ ጥረት ሲያደርጉ፣ የፋሽስት መንግሥት ወንጀለኛነት በይፋ ተገልጦ በፍጥነት እርምጃ እንዲወሰድበት፣ ከታላላቅ አገሮች መካከል የታገለው አንቶኒ ኤደን ብቻውን እንደነበረ አይረሳም።
- በሊግ ኦፍ ኔሽን ሕግ በአንቀጽ 16 መሠረት፣ በግፈኛው መንግሥት ላይ ስለሚወሰደው የኢኮኖሚ ዕገዳ ዝርዝር ጥናት ሲደረግ፣ ጉዳት የሚያስከትሉት የነዳጅ ዘይትና ብረታ ብረት የመሳሰሉትን ሁሉ እንዲጨመሩ፣ አንቶኒ ኤደን ከካናዳው መልዕክተኛ ጋር ሆኖ ያደረገው ሙከራ ባይሳካለትም፣ ለኢትዮጵያ ያሳየው ድጋፍ አይዘነጋም።
- ዱቼ ሙሶሊኒና የገቤሹ እንደራሴው ባሮን አሉይዚ በሚለዋወጧቸው ኮሬስፖንዳንሶች፣ ዋናው ጠላታችን የእንግሊዝ መንግሥት ሳይሆን፣ አንቶኒ ኤደን ነው እያሉ እንደዚያ ሲተቹትና እንደዚያ ሲያወግዙት፣ ከዕምነቱ ሳይዛነፍ ምንም ዓይነት ግምት እንዳልሰጣቸው ሳይጠቀስ የሚታለፍ አይደለም።

እንግዲህ ! በፖለቲካው ዓለም፣ የትናንቱ ሐሳብ ለዛሬው፣ የዛሬው ደግሞ ለነገው ሊያገለግል ስለማይችል፣ የአንቶኒ ኤደን አቋም መልኩን የለወጠው፣ ያለጥርጥር የጊዜው የፖለቲካ ሁኔታ አስገድዶት እንጂ፣ ከራሱ መሠረታዊ ዕምነት ተዛንፎ ነው ማለት አይቻልም። ይኸ የአሥራ ስድስተኛው የሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ከመጀመሩ ሦስት ሳምንት በፊት፣ ሁለት ዋና ዋና የሆኑት የታላቋ ብሪታንያ የኮንሰርቫተር ፓርቲ አባሎች፣ ኔቪል ቻምበርሌንና ዊንስተን ቸርችል (Neville Chamberlain and Winston Churchill) በሰጡት መግለጫ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን በጣልያን ላይ ያወጀው የኢኮኖሚ ዕገዳ ምንም ውጤት ስላልሰጠ፣ መቀጠሉ የሚያስፈልግ አለመሆኑን አጥብቀው ተናግረዋል። ቸርችል፣ የኢኮኖሚው ዕገዳ በትክክል ሳይፈጸም በመቅረቱ ፍሬ ቢስ መሆኑን ሲገልጽ፣ ቻምበርሌን ደግሞ፣ በዚህ ሁኔታ የኢኮኖሚውን ዕገዳ መቀጠል እንደ እብደት የሚቆጠር እርምጃ ነው፣ እስከ ማለት ደርሷል። በዚህ አኳኋን፣ ዋና ዋናዎቹ የታላቋ ብሪታንያ የፖለቲካ መሪዎች አስተያየታቸው ወደዚህ መልክ ካዘነበለ፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ኤደን፣ ከእነሱ የተለየ ፖሊሲ ይዞ መቀጠል አይችልም።

ይሁን እንጂ፣ ኢትዮጵያ በሙሶሊኒ ከተያዘች ከሁለት ወራት በኋላ፣ አንቶኒ ኤደን ያ የማይበገረው ኃይለኛ ፀረ ፋሽስትነቱ እጅግ ለስልሶ፣ በፋሽስት ላይ የተወሰነው የኢኮኖሚ ቅጣት እንዲቆም፣ ከመንግሥታት እንደራሴዎች መካከል የመጀመሪያው ሐሳብ አቅራቢ ሆኖ ሲታይ፣ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴና መልዕክተኞቻቸው አሳድረውበት የነበረውን ተስፋ ምን ያህል እንዳጨለመባቸው መገመት ይቻላል። ኤደን በሰጠው መግለጫ ውስጥ፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል መንግሥታት በኢትዮጵያ ላይ የጣልያንን ይዞታ ዕውቅና እንዳይሰጡ አጠንክሮ መናገሩ ደስ የሚያሰኝ ቢሆንም፣ በኢኮኖሚው እገዳ ምትክ፣ በግፍ የተያዘውን የኢትዮጵያን ነጻነት ለማስመለስ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን ምን እርምጃ መውሰድ እንደሚገባው አንዳች ሐሳብ ባለማቅረቡ፣ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴን እና መልዕክተኞቻቸውን ቅር አሰኝቷል። እንደሚታወቀው፣ የአንድ መንግሥት ፖሊሲ እንደ ጊዜው ሁኔታና ለአገሩ እንደሚያስገኘው ጥቅም መለዋወጡ የማይቀር ስለሆነ፣ እንደ መጽሐፍ ቅዱስ ለምን ጊዜውም ፀንቶ ይኖራል ብሎ ማሰብ

አይቻልም። በዚህ ትክክለኛ ፍርድ በተነፈገው የኢትዮጵያ ጉዳይ፣ እስካሁን የተመለከትነው፣ የታላቋ ብሪታንያን መንግሥት አቋም ብቻ ሲሆን፣ አሁን ደግሞ ሌሎች አገሮች ምን አስተያየት እንደገለጹ እናያለን።

## የፈረንሣይ ሶሲያሊስት መንግሥት ጠቅላይ ሚኒስትር ሌዎን ብሉም (Léon Blum)

እ.ኤ.አ በጥር 1936 ዓ.ም፣ የፒየር ላቫል መንግሥት ሲወድቅ፣ በምትኩ የተመረጠው ጠቅላይ ሚኒስትር አልቤርት ሳሮ፣ (Albert Sarraut) በ1935 ዓ.ም ሙሶሊኒና ላቫል በኢትዮጵያ ላይ ያደረጉትን ስምምነት አክብሮ እንደ ጠበቀ፣ ከስድስት ወራት በኋላ ከሥልጣን ተሰናበተ። ለምሳሌም ያህል፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት ከጦርነቱ በፊት ከአውሮፓ የገዛቸው የጦር መሣሪያዎች፣ በላቫልና በሙሶሊኒ ስምምነት መሠረት ጂቡቲ ላይ ተይዘው ስለነበረ፣ እንዲለቀቁ በሊግ ኦፍ ኔሽን የተወሰነውን አልፈጽምም ብሎ፣ በመጨረሻውም በባቡር አሳፍሮ ለፋሽስት ያስረከበው ይኸው የ " ሳሮ " መንግሥት ነበር።

እ.ኤ.አ በሰኔ 1936 ዓ.ም፣ ፈረንሣይ አገር በደረሰው "ሕዝባዊ ግንባር" በተባለው (Front Populaire) ከፍተኛ የፖለቲካ ለውጥ፣ የቀኝ ወገኖች የነበሩት ሁሉ ወድቀው የግራ ክንፎች ዕድል ስለአገኙ፣ ሌዎን ብሉም (Leon Blum) የተባለው የሠራተኛው ክፍል መሪ፣ የራዲካሎቹን፣ የሶሲያሊስቶቹንና የኮሙኒስቶቹን ድጋፍ አግኝቶ፣ አዲስ መንግሥት አቋቋመ። በዚህ ጊዜ፣ የቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ የፖለቲካ አማካሪዎች የሆኑት ሁሉ፣ ይህ በፈረንሣይ አገር የተደረገው የፖለቲካ ለውጥ፣ በግብሩ ፀረ ፋሽስትነቱ የተረጋገጠ ስለሆነ፣ እስከ ዛሬ ኢትዮጵያ የደረሰባትን ጉዳት ሊክሳት ይችላል የሚል ትልቅ ተስፋ አሳድረው ነበር። አዲሱ ጠቅላይ ሚኒስትር ሌዎን ብሉም፣ የግራ ክንፍ የሆነውን መንግሥት ካቋቋመ በኋላ፣ ለመጀመሪያ ጊዜ የፈረንሣይን የውጭ ፖሊሲ ተንትኖ ለማስረዳት የቀረበው፣ በዚህ በሊግ ኦፍ ኔሽን አሥራ ስድስተኛው ጠቅላላ ስብሰባ ላይ ነው። አጋጣሚም ሆኖ፣ የዚህ ጉባኤ ትልቁ አጀንዳ፣ የአጥቂው የሙሶሊኒ ጣልያንና የተጠቂዋ የኢትዮጵያ ጉዳይ ስለሆነ፣ ሌዎን ብሉም ምን አስተያየት እንደሚገልጽ፣ ወይም ምን ሐሳብ እንደሚያቀርብ ለመስማት በናፍቆት የተጠበቀው፣ በባለጉዳዮቹ በቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ መልዕክተኞች ዘንድ ብቻ ሳይሆን፣ በመላው የአምሳዎቹ የመንግሥታት እንደራሴዎች ጭምር ነው፣ ለማለት ይቻላል። ሌላው ቀርቶ ኢትዮጵያ የአባልነት መብቷ ተጠብቆ እስከቆየላት ድረስ፣ የፋሽስት መንግሥት ለሊግ ኦፍ ኔሽን ጉባኤ መልዕክተኛዬ አይካፈልም ብሎ ቢወስንም፣ የነላቫል ተቃዋሚ ነው የተባለው አዲሱ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር የሚናገረውን ለማዳመጥ፣ በስዊስ ያለው የጣልያን አምባሳደር ዲፕሎማቶቹን አስከትሎ በአዳራሹ ጋለሪ ላይ ተገኝቶ ነበር።

አዲሱ የፈረንሣይ መንግሥት መሪ ባደረገው ረዥም ንግግር ውስጥ፣ በአውሮፓ ላይ ያለውን ጠቅላላ ሁኔታና አሳሳቢ የሆኑትንም ጉዳዮች በየመልኩ እየዘረዘረ ሲያስረዳ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን ሚናው ምን መሆን እንደሚገባው፣ ግልጽና መሠረታዊ የሆነ ሐሳብ ለመስጠት የተዘጋጀ መስሎ አልታየም። በሌዎን ብሉም ዲስኩር ውስጥ የተለቀሙት ፍሬ ነገሮች የሚከተሉት ነበሩ።

" ... የፈረንሣይን መንግሥት እንድመራ ከተመረጥኩበት ከጥቂት ሳምንታት ወዲህ፣ እንደምሰማውና እንደማነበው፣ አገሬ በኢንተርናሽናል መስክ ላይ የነበራት ከፍተኛ ቦታ ወደ ሁለተኛ ደረጃ እያዘቀዘቀ፣ የዓለምን ሕግ የሚጥሰውንና

የሰላም ጠንቅ የሆነውን ሁሉ ለመቋቋም ደካማ ሆናለች እየተባለ ይነገራል። ይህ አስተያየት ምን ያህል ቅሬታ እንደሚያሳድርብኝ ሳትገነዘቡት አትቀሩም። እኔ ዛሬ መንግሥቷን ተረክቤ በኃላፊነት የማገለግላት ፈረንሣይ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን እና በኢንተርናሽናል መስክ ላይ፤ የአንዱ መንግሥት ደረጃ ከአንዱ የሚበልጥ ወይም የአንዱ ሐሳብ ከአንደኛው በተሻለ የሚደመጥ ነው ብላ የምታምን አለመሆኗን ማረጋገጥ እፈልጋለሁ። ምናልባት፤ ዕምነቷንም ሆነ ዓላማዋን አጉልታ የምታሳየው፤ ለዓለም ሰላምና ለሕዝቦች ደህንነት የኢንተርናሽናል ሕጐች እንዲከበሩ ካልሆነ በስተቀር፤ ለራስ ጥቅም በማሰብ ወይም በደካማነት መንፈስ የምትወስደው እርምጃ አለመኖሩ መታወቅ አለበት። በዚህም መሠረት፤ በአሁኑ ሰዓት በአውሮፓው ዓለም የተንጠለጠለውን አደጋ፤ የፈረንሣይ ሕዝብ እንዴት ባለ ሥጋት እንደሚመለከተውና ምን መስሎ እንደሚታየው ልገልጽላችሁ እወዳለሁ።

> **የፈረንሣይ ሕዝብ፤ በማንም አገር መንግሥት አስተዳደርና አስተሳሰብ ውስጥ ሳይገባ፤ አጥብቆ የሚፈልገውና ከፍ ያለ ጥረት የሚያደርገው፤ በዓለም ላይ ሰላም እንዲሰፍን ብቻ ነው።**

> ያለንበት ዓለም የሰላም ዓለም አይደለም። የዚህም ምክንያቱ ምን እንደሆነና አሥጊነቱም ለምን ያህል ጊዜ እንደሚቀጥል መመራመርን አልፈልግም። **ሐቁ ግን የሚያሳየን አደጋው ከፊታችን መደቀኑን ነው።**

> ከአሥራ ስምንት ዓመታት ወዲህ በዛሬው ሰዓት የምናየው የአውሮፓ ሁኔታ፤ ለጦርነት የተመቻቸ ሆኖ መገኘቱን ነው። ይህንንም አደጋ እያከበደ የሚያመለክተን፤ አንዳንድ አገሮች በስውር የጦር ኃይላቸውን ለማዳበር እሽቅድድም ላይ መሆናቸው ነው።

> የፈረንሣይ ሕዝብ፤ ለአለንበት ዓለም የሚያዋጣን ለሰላም መሥዋዕትነትን መቀበል ነው በማለት የሚያደርገው ጭንቀት፤ ለኃይለኞችና ለሕገ ወጦች መንግሥታት ድክመትን እንደ ማሳየት ሊቆጠርበት አይገባም። **በማናቸውም መስክ ሰላም ሊሰፍን የሚችለው፤ የኢንተርናሽናልን ሕግና ሥርዓት በማክበር በትዕግሥት በሚደረግ ጥረት ነው።**

> **ከዚህ ቀጥዬ ላሳስብ የምወደው፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል መንግሥት በሆነችው በኢትዮጵያ ላይ የደረሰው አሳዛኝ ሁኔታና፤ ከዚህም የሚገኘው ትምህርት፤ ችላ የሚባል አለመሆኑን ነው። የዓለምን ሰላም ለመጠበቅ ሲሉ፤ ታላላቅ አገሮች አዘጋጅተው ያጸደቋቸውን ሕጐችና ስምምነቶች፤ አምባገነኖች እየተነሡ ሲያፈርሱና ችግር ሲፈጥሩ፤ ሰላምን እቦታው ለመመለስ የሰላም ንግግር በማድረግ መፍትሔ ለመስጠት ካልተቻለ፤ የጦርነት እርምጃ መውሰድ ነበረባቸው ...** ካለ በኋላ፤ ሌዎን ብሉም ለንግግሩ ማሰሪያ ያደረገው፤ " ... **የዓለም ሕዝብ ሰላም ፈላጊ ነው። ሠርቶ ለፍቶ ቀኑን ካሳለፈ በኋላ፤ ማታ የሚጠብቀው ሰላም የሰፈነበትን የዕንቅልፍ ጸጋ ለማግኘት ነው። ለዚህም ተስፋ የሚያደርገው በሊግ ኦፍ ኔሽን ላይ ስለሆነ፤ ጌቶቼን የማሳስባችሁ፤ የዓለም ሕዝብ የጣለባችሁ ዕምነት ምን ያህል ከፍተኛ መሆኑን ተገንዝባችሁ፤ ቅር እንዳታሰኙት መጠንቀቅ ያለባችሁ መሆኑን ነው ...** " በሚል ቃል ነበር።

እንግዲህ ! ፍሬ ነገሮቹ ከዚህ በላይ ባጭሩ እንደ ተጠቀሱት፤ የፈረንሣይ ሶሲያሊስት መንግሥት መሪ የሆነው ሌዎን ብሉም፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ሸንጎ ላይ

ባደረገው ዲስኩር ውስጥ፤ ስለ ኢትዮጵያና ስለ ጣልያን ጉዳይ በመጠኑ ከማውሳት በስተቀር፤ ግልጽና ተጨባጭ የሆነ ሐሳብ አላቀረበም። በተለይም ቀደም ሲል እንደ ተገለጸው፤ የዚህ የሊግ ኦፍ ኔሽን አሥራ ስድስተኛው ጠቅላላ ጉባኤ ዋናው አጀንዳ፤ የአንድን አባል አገር ነጻነት በገፈፈው አጥቂ መንግሥት ላይ ከዚህ ቀደም የተደረገው የኢኮኖሚ ጭቆና እንዲቀጥል ወይም እንዲሰረዝ፤ ወይም ደግሞ ሌላ ምን ዓይነት እርምጃ መውሰድ እንደሚያስፈልግ ተነጋግሮ ለመወሰን ነው። ስለዚህ፤ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር አቋሙ ምን እንደሆነ በትክክል ገልጾ አለመናገሩ፤ እጅግ የሚያሳዝን ነው እየተባለ ብዙ ትችት ተሰጥቶበት ነበር።

ሌዎን ብሉም በተናገረ በሦስተኛው ቀን፤ (ሐምሌ 3 ቀን 1936 ዓ.ም) የሶሲያሊስቱ መንግሥት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ኢቮን ደልቦስ (Yvon Delbos) የጠቅላይ ሚኒስትሩን ዲስኩር በተሻለ መንገድ ማብራራት የሚጠቅም መስሎት የሚከተለውን ተናገረ። " ... ባለፉት ወራቶች በአባል አገሮች መካከል በደረሰው አሳዛኝ ድራማ የመንግሥታት ማህበር የወሰደው እርምጃ ሳይሳካ የቀረው፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን መሠረታዊው ሕግ ምክንያት ሳይሆን፤ በአባል መንግሥታት በኩል በአፈጻጸም የደረሰ በደል መሆኑ መታወቅ አለበት። ... ፈረንሣይ የሊግ ኦፍ ኔሽን መሠረታዊ ሕግ መሻሻል ይገባዋል የሚባለውን ሐሳብ አትቀበልም። ፕሮብሌሙ ሕጉ አይደለም። ስለዚህ፤ ፈረንሣይ የምታምነው በሕጉ መሠረት የሚደረጉት ውሳኔዎች በተግባር ላይ እንዲውሉ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን አስፈጻሚ ኃይል እንዲኖረው ተገቢውን ዘዴ መፈለግ ብቻ ነው ... " ሲል ንግግሩን ፈጸመ።

እንደሚታየው፤ አሁንም ቢሆን የፈረንሣይ አቋም ምን እንደሆነ በግልጽ ሊታወቅ አልቻለም። በጉባኤው ገበታ ላይ ለውሳኔ የቀረበው የኢትዮጵያ ጉዳይ፤ ትልቁ ጥያቄ በጣልያን ላይ የተወሰደው የኢኮኖሚ ጭቆና ይቀጥል ወይስ አይቀጥል ነው። ለዚህ ትክክለኛውን መልስ በመስጠት ፋንታ፤ አዲሱ የፈረንሣይ መንግሥት የሚናገረው፤ የኢኮኖሚው ጭቆና ሳይሳካ ቀርቶ ውጤት ያልሰጠው፤ አባል አገሮች ውሳኔውን በትክክል በተግባር ሳያውሉት መቅረታቸውን ነው። እሺ ! ታዲያስ ? ዛሬ ምን ይደረግ ? ... ለዚህ ጥያቄ ፈረንሣይ መልስ የላትም። በኢትዮጵያ ላይ ሙሶሊኒ የፈለገውን ማድረግ የቻለው፤ የተወሰደበትን የኢኮኖሚ ዕገዳ ውሳኔ፤ አባል አገሮች በትክክል ባለመፈጸማቸው ብቻ አይደለም። የኢኮኖሚው ዕገዳ እንደ ነዳጅ ዘይትንና ብረታ ብረት የመሳሰሉትን እንዳይጨምርና፤ በፋሽስቱ መንግሥት ላይ ጉዳት እንዳይደርስ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ኮሚቴ ላይ ከፍ ያለ ጥረት አድርጎ ያስወሰነው፤ ከሌዎን ብሉም በፊት የነበረው የፒየር ላቫል መንግሥት መሆኑ መረሳት የለበትም። የትናንቱም ሆነ የዛሬው መንግሥት ያው በፈረንሣይ ስም ሆኖ የሚሠራ ስለሆነ፤ ለዚች ለተበደለች ኢትዮጵያ የሚያስፈልጋትን ትክክለኛ ፍርድ ማግኘት ብቻ ነበር። ይህንንም ትናንትም ሆነ ዛሬ ማግኘት ስላልቻለች፤ ኢትዮጵያ በፈረንሣይ መንግሥት የተፈጸመባትን በደል፤ ለምንጊዜውም በታሪኳ ሳትጠቅሰው ማለፍ አትችልም። ንጉሠ ነገሥቷ በዚያ እጅግ አሳዛኝ በሆነውና ልባዊ ስሜትን ባዘለው አቤቱታቸው፤ " ... እግዚአብሔርና ታሪክ ፍርዳችሁን ሲያስታውሱት ይኖራሉ ... " ብለው የተናገሩት፤ ትንቢታቸው ደርሶ፤ ኢትዮጵያ የማየት ዕድል ሲያጋጥማት ወደፊት እንደርስበታለን።

## የሶቪየት ሕብረት መንግሥት ዋና መልዕክተኛ፣
## ሚስተር ሊት ቪኖፍ (Litvinoff)

" ... ዛሬ እዚህ የተሰበሰብነው የሊግ ኦፍ ኔሽንን የአንድ ገጽ የሕይወት ታሪክ መራራ በሆነ ስሜት እንብበን፣ መደምደሚያውን ለመስጠት ነው ... " ካለ በኋላ፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ስላለው ጦርነት፣ የሶቪየት ሕብረት ሶሲያሊስት መንግሥት ያለውን አስተያየት እና ሊግ ኦፍ ኔሽን ምን እርምጃ መውሰድ እንዳለበት የሚያምንበትን ሐሳብ ደህና አድርጎ አስረድቷል። ለሠላሳ ደቂቃዎች ባደረገው ሰፊ መግለጫ፣ ስለ ኢትዮጵያ ከተናገረው ውስጥ ዋና ዋናዎቹ ፍሬ ነገሮች ከዚህ የሚከተሉት ናቸው።

- « ... ማህበርተኛችን የሆነችውን የኢትዮጵያን ነጻነት ለማስከበር፣ በአጥቂው ማህበርተኛችን በጣልያን መንግሥት ላይ የኤኮኖሚ ጭቆና እንዲደረግ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ የወሰነውን፣ እያንዳንዳችን ግዴታችንን አሟልተን መፈጸም ወይም አለመፈጸማችን ተለይቶ እንዲታወቅና ወቀሳውንም ሆነ ምስጋናውን ለመቀበል ዝግጁ መሆን አለብን።

- እኔ የምወክለው የተባበረው የሶቪየት ሕብረት ሶሲያሊስት መንግሥት፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ጠቡ ከተጀመረበት አንሥቶ እስከ ዛሬ ድረስ ያሳየው የማያወላውል አቋም፣ ለዓለም ሕዝብ ሰላምና ደህንነት የጋራ ፀጥታን ለማስከበር በተቋቋመው የመንግሥታት ማህበር ዓላማ ላይ ተመርኩዞ መሆኑን ማንም ሊክደው አይችልም። እኛ የሶቪየት ሕብረት ሶሲያሊስት መንግሥት፣ ከኢትዮጵያ ንጉሣዊ መንግሥት ጋር የዲፕሎማቲክ ሆነ የጥቅም፣ ምንም ዓይነት ግንኙነት የለንም። ነገር ግን፣ በተለያየ መስክ ብዙ ግንኙነቶች ባሉን በጣልያን መንግሥት ላይ የምንፈርድበትና እርምጃ የምንወስድበት፣ የኢትዮጵያን ነፃነት በመግፈፍ የፈጸመው ግፍ የሊግ ኦፍ ኔሽንን ሕግ በመጻረር መሆኑን ስለምናምንበት ነው። በዚህ ጉዳይ ላይ ያለው አቋማችን ዛሬም አልተለወጠም።

- የኢትዮጵያ ሕዝብ በጀግንነት ለነጻነቱ የሚያደርገውን ተጋድሎ እስከሚቻለው ድረስ ያላቋረጠ ቢሆንም፣ የጣልያን የጦር ኃይል ከግማሽ በላይ የሆነውን የአገሩን ግዛት በመያዙ፣ ይኸው እንደምናየው ንጉሡና መንግሥታቸው ከአገር ወጥተዋል። ስለዚህ፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን በኩል በአጥቂው ላይ እስከዛሬ የተደረገው የኤኮኖሚ ጭቆና ውጤት መስጠት ስላልቻለ፣ ከዚህ የበለጠ የጠነከረ እርምጃ መውሰድ ግዴታ ይሆናል። ይህም በቂ ሆኖ ካልተገኘ፣ በጦር ኃይል እስከ መጠቀም ለመድረስ አስፈላጊነቱ መታሰብ አለበት።

- የሶቪየት ሕብረት ለመላው የመንግሥታት ማህበር አባላት አጥብቆ የሚያሳስበው፣ በደረሰው ጉዳይ የኃላፊነት ስሜቱ ቀስቅሶት፣ የኢትዮጵያን ነጻነት ለማስመለስና የሊግ ኦፍ ኔሽንን መሠረታዊ አቋም ለማዳን፣ በአጥቂው መንግሥት ላይ የጠነከረ እርምጃ እንዲወሰድ ነው። እስከዛሬ እንደታየው፣ የኢትዮጵያ ጉዳይ ምንም ሳይደረግለት

**በችሎታ ሞቶ እንዲቀበር ከተደረገ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽንም የሕይወቱ ፍጻሜ ሆኖ አብሮ ሊቀበር እንደሚችል ማሰብ ያስፈልጋል ... »**

ከዚህ በላይ እንደታየው፤ ከሶቪየት ሕብረት ሶሲያሊስት መንግሥት የተሰጠው መግለጫና የቀረበው ሐሳብ፤ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴና መልዕክተኞቻቸው የጠበቁት አልነበረም። ሙሴ ሊትቪኖፍ በተናገረው ውስጥ እንደ ጠቀሰው፤ በምኒልክ ዘመን፤ ከሩሲያው የዛር ንጉሥ ጋር የነበረው ትልቅ የወዳጅነት ግንኙነት፤ የኮሙኒዝም አስተዳደር ከተመሠረተ ወዲህ ተቋርጦ የሚኖር ነው። ይሁን እንጂ፤ የፋሽስት መንግሥት የወልወልን ግጭት ምክንያት አድርጎ ኢትዮጵያን ማጥቃት ከጀመረበት ጊዜ አንስቶ፤ የሶቪየት ሕብረት የኢትዮጵያን አቋም ከመደገፍ አላቋረጠም። በሊግ ኦፍ ኔሽን የቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ዋና መልዕክተኛ የነበሩት ፊታውራሪ ተክለ ሐዋርያት፤ በትምህርት ያደጉት በመስኮብ አገር ስለሆነ፤ ከሊትቪኖፍ ጋር የሞቀ የወዳጅነት ግንኙነት ስለነበራቸው፤ የሶቪየቱ መልዕክተኛ በተለይ በገቤኝ የሊጉን ምክር ቤት በሊቀመንበርነት በሚመራበት ጊዜ፤ ለኢትዮጵያ ድጋፉን ከመስጠት አልተቆጠበም ነበር። አሁንም፤ ኢትዮጵያ በጠላት እጅ ተይዛ፤ ወዳጆቿ የነበሩት አገሮች ሁሉ ችላ ብለዋት ለየራሳቸው ጥቅም በሚሠሩበት ጊዜ፤ የሶቪየት ሕብረት መንግሥት፤ ፋሽስትን በብርቱ በመቃወም፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ላይ የተናገረውና የሰጠው ድጋፍ፤ በኢትዮጵያ ታሪክ ውስጥ ምስጋና ሊያገኝ የሚገባ ነው።

## የቻይና ዋና መልዕክተኛ፤
## ዶክተር ዌሊንግቶን ኩ (Dr. Wellington Koo)

ኢትዮጵያ በተፈጸመባት በደል የቻይና መንግሥትና ሕዝብ ምን ያህል እንደሚያዝን ስሜቱን ከገለጸ በኋላ፤ ዶክተር ኩ (Dr. Koo) ባቀረበው ሐሳብ፤ " ... የመንግሥታት ማህበር አባል አገሮች፤ የዓለም ሰላምና ፀጥታ ተከብሮ እንዲኖር ምን ማድረግ እንደሚገባቸው፤ ከእኔ በፊት የሶቪየት ሕብረት ዋና መልዕክተኛ ደህና አድርጎ ተናግሮታል። **አሁንም ኢትዮጵያን በወረረው በአጥቂው መንግሥት ላይ የተወሰነው የኢኮኖሚ ዕገዳ፤ ውጤት የማይሰጥ ከሆነ፤ በጦር ኃይል ለመጠቀም አስፈላጊነቱን ማሰብ ያስፈልጋል ...** " ብሏል።

## የደቡብ አፍሪካ ዋና መልዕክተኛ፤
## ሚስተር ቲ ዋተር (Te. Water)

" ... በአሁኑ ሰዓት አምሳዎቹ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች ከሦስት በማይበልጡ ታላላቅ መንግሥታት እየተመሩ፤ አንዲት ደካማ የሆነችውን አገር ለመርዳትና ነጻነቷን ለማዳን፤ ከእንግዲህ ወዲህ በአጥቂው መንግሥት ላይ የሚወስዱት እርምጃ አለመኖሩን ለመወሰን ተዘጋጅተው ይታያሉ። **ይህ ሁኔታ በግልጽ የሚያመለክተው፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን መሠረታዊ አቋምና ተግባር ወደ መፍረስ ማዘንበሉን ነው።** ... የኢትዮጵያ ነጻ መንግሥትነት መደምሰስና በጣልያን የጦር ኃይል መያዝን፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን በምንም መንገድ ሊቀበለው የማይገባና እኛም አባል አገሮች ባለን አቅምና ችሎታ ሁሉ ተቃውሞአችንን ማጠንከር ግዴታችን ነው። ... እኔ የምወክለው መንግሥት የሰጠኝን መምሪያ በመከተል፤ **ባለፈው ጥቅምት ወር 1935 ዓ.ም አምሳዎቹ መንግሥታት በአንድ ቃል**



እ.ኤ.አ ማክሰኞ ግንቦት 5 ቀን 1936 ዓ.ም የማርሻል ባዶሊዮ ጦር አዲስ አበባን ሲይዝ፤ ሙሶሊኒ በሮም በሚገኘው በፒያሳ ቬኔሲያ አደባባይ መቶ ሺህ ሕዝብ ሰብስቦ፤ ፎቶግራፉ እንደሚያመለክተው በደስታ ፈነጨ።

" ... ለመላው የጣልያን ሕዝብ እናገራለሁ። ለመላው የዓለም ሕዝብ አስታውቃለሁ። በዛሬው ዕለት ከእኩለ ቀን በኋላ በአሥር ሰዓት ማርሻል ባዶሊዮ በላከልኝ ቴሌግራም፤ ጀግናው የጣልያን የጦር ሠራዊት በድል አድራጊነት አዲስ አበባ መግባቱን የምሥራች ልኮልኛል። እንግዲህ! ከዛሬ ጀምሮ ኢትዮጵያ የጣልያን ሆናለች ... "

ቤኒቶ ሙሶሊኒ 5/05/36

ተስማምተው በአጥቂው መንግሥት ላይ የወሰኑት የኤኮኖሚ ዕገዳ፤ ጥብቅ በሆነ አፈጻጸም እንዲቀጥል ለጉባኤው እገልጻለሁ ... " ብሏል።

## የስዊድን መልዕክተኛ
## ወ/ት ሔሰልግሪን (M^LLE Hesselgren)

" ... በዚህ ስብሰባ ላይ እስካሁን የተደረጉትን ከፍተኛና አስደናቂ የሆኑትን ዲስኩሮች፤ በጥንቃቄ አዳምጫለሁ። በጣም የማዝነው፤ ከእነዚህ ዲስኩሮች ውስጥ፤ አንዳቸውም የተስፋ ጉዳና የሚከፍቱልን ሆነው ባለማግኘቴ ነው።

... አምሳዎቹ መንግሥታት፤ ለአጥቂውና ለሕገወጡ መንግሥት የሚፈልገውን እንዲያደርግ መንገድ ሲከፍቱለት ይታያሉ።

... አምሳዎቹ መንግሥታት አንድ ደካማ የሆነችውን አገር፤ በአንድ ሕገወጥ በሆነ መንግሥት፤ ነጻነቷ ሲገፈፍና ከዓለም ካርታ ላይ ስትፋቅ ዝም ብለው ይመለከታሉ።

ባለፈው ጥቅምት ወር 1935 ዓ.ም አምሳዎቹ መንግሥታት፤ በሕገ ወጡ መንግሥት ላይ እርምጃ ለመውሰድ ያሳዩት አንድነትና ጥንካሬ ከፍ ያለ ተስፋ የሚሰጥ መስሎ ታይቶ ነበር። በዚህም ምክንያት፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን ከዚህ ቀደም ለታናናሽ አገሮች ያላሳየውን ድጋፍና ተገንነት፤ አሁን በተግባር ለማዋል መጀመሩ ነው ተብሎ በብዙዎች ዘንድ ያሳደረው ዕምነት፤ ሳይቀጥል በመቅረቱና ዛሬ ውጤቱ ባዶ ሆኖ መገኘቱ፤ እጅግ የሚያሳዝንና ተስፋ የሚያስቆርጥ ነው።

እንግዲህ ! ዛሬ በአለንበት ዓለም፤ ታናናሽና ደካሞች የሆኑት መንግሥታት ሁሉ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ዘንድ ለነጻነታቸውና ለፀጥታቸው ምንም ዓይነት ዋስትና እንደሌላቸው ቢያውቁት አይሻልም ወይ ? የሚል ጥያቄ ስለሚቀርብ፤ መልሱ እንዲታሰብበት አስፈላጊ ይሆናል ... "

## የሜክሲኮ ዋና መልዕክተኛ፤
## ሚስተር ባሶል (Mr. Bassols)

" ... ባለፈው ጥቅምት ወር 1935 ዓ.ም. በጣልያን ላይ ለሚደረገው የኤኮኖሚ ዕገዳ፤ በተቋቋመው የአሥራ ስምንት አገሮች ኮሚቴ ውስጥ ሜክሲኮ አባል በመሆኗ፤ የሚወሰኑት ቅጣቶች የጠነከሩና አጥቂው መንግሥት የጀመረውን ጦርነት እንዲያቆም የሚያስገድዱት እንዲሆኑ፤ ተሟግታ ነበር። ይሁን እንጂ፤ ሜክሲኮ ያላት ድምፅ አንድ ብቻ ስለሆነ፤ በኤኮኖሚው ዕገዳ ውስጥ የነዳጅ ዘይት እንዲጨመር ያቀረበችው ሐሳብ በቂ ድጋፍ ሳያገኝ ቀረ። ከዚህም በላይ ሌሎቹ የተወሰኑት ዕገዳዎች በአባል አገሮች ዘንድ በትክክል አለመፈጸማቸው፤ ካለፈው መጋቢት 1936 ዓ.ም ጀምሮ የታወቀ ሲሆን፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን በኩል አንዳች እርምጃ አልተወሰደም። ይህ ሁኔታ ቀስ በቀስ እየተጋለጠ፤ የመንግሥታት ማህበርን ከፍ ያለ ችግር ላይ እንደሚጥለውና እንደሚያስወቅሰው፤ ሜክሲኮ እየደጋገመች አሳስባ እንደነበረ ለማስታወስ እፈልጋለሁ።

ሜክሲኮ፣ ሕገ ወጡ መንግሥት በኢትዮጵያ ሕዝብና መንግሥት ላይ ባደረሰው ጥቃት ጥልቅ ኃዘን ይሰማታል። ነገር ግን፣ ሜክሲኮ ብቻዋን ብታዝንና ብትቆረቆር ምን ውጤት ታመጣለች ? ... የጂዮግራፊ አቀማመጧ፣ የሕዝቧ ብዛት፣ የኢኮኖሚዋ ልማት፣ የጦር ኃይሏ ድርጅት፣ ምንም ለማድረግ አያመቻትም። ስለዚህ፣ ዕምነቷን የምታሳርፈውና የምትመኘው፣ መላው የመንግሥታት ማህበር አባሎች መከራው የወደቀባትን አገር ከሥቃይዋ ለማዳን፣ የተባበረና የጠነከረ እርምጃ እንዲወስዱ ብቻ ነው ... "

ከዚህ በላይ እንደ ቀረበው፣ ለኢትዮጵያ ያላቸውን የኃዘን ስሜት ከገለጹት የተወሰኑ አገሮች መካከል፣ በፋሽስት መንግሥት ላይ የተፈረደው የኢኮኖሚ ቅጣት ውጤት ካልሰጠ፣ በጦር ኃይል ጭምር እርምጃ እንዲወሰድ መታሰብ ያለበት መሆኑን በይፋ የተናገሩት፣ የሶቪየት ሕብረትና የቻይና መልዕክተኞች ብቻ ናቸው። ሌሎቹ እንደሜክሲኮ፣ እንደ ደቡብ አፍሪካና እንደ ኒውዚላንድ የመሳሰሉት በጣት የሚቆጠሩ ጥቂት አገሮች፣ በሕገወጡና በአጥቂው ላይ የኢኮኖሚው ጭቆና እንዲቀጥል ቢያመለክቱም፣ ከአምሳ ሁለቱ አባል መንግሥታት መካከል ከሙቶ ዘጠናዎቹ የታላቋ ብሪታኒያ ዋና መልዕክተኛ፣ ግንባር ቀደም ሆኖ ዕገዳው እንዲነሣ ያቀረበውን ሐሳብ የሚደግፉ ሆኑ። በዚህ ጊዜ በኢትዮጵያ ጠላት ላይ የሚወሰድ አንዳች እርምጃ እንደሌለ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልዕክተኞች ሲገነዘቡ፣ በቶሎ ፈጥነው ሁለት ዓይነት የሕግ ረቂቅ ውሳኔዎች አዘጋጅተው ጉባኤው እንዲያጸድቅላቸው አቀረቡ። የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊ ምንም እንኳ የኢትዮጵያ መልዕክተኞች መሪ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ናቸው ብሎ ቢመዘግባቸውም፣ ንጉሠ ነገሥቱ ደግሞ በበኩላቸው፣ የመልዕክተኞቹ መሪ የሐረር እንደራሴ ደጃዝማች ነሲቡ ዘአማኤል ነው ብለው አስታወቁ። በዚህም መሠረት፣ ከኢትዮጵያ በኩል የተዘጋጁትን ሁለት ረቂቅ ውሳኔዎች ለጉባኤው ለማቅረብ ደጃዝማች ነሲቡ ሊቀመንበሩን ሲጠይቁ፣ የቤልጂየሙ ጠቅላይ ሚኒስትር ሙሴ ቫን ዚላንድ (Van Zeeland) በመጀመሪያ ከጉባኤው ቢሮ የሚቀርብ ሐሳብ ስለአለ፣ መጠበቅ አለብህ ብሎ ከለከላቸው።

በደንቡ መሠረት፣ የኮንፌራንሱ ቢሮ ረቂቅ ውሳኔ አዘጋጅቶ ማቅረብ ያለበት፣ የጠቅላላው ጉባኤ ሥራ ሲጠናቀቅ እንጂ፣ የአባል አገሮችን ሐሳብ ለማጨናገፍ በማህል ጣልቃ መግባት የለበትም በማለት፣ የንጉሠ ነገሥቱ የፖለቲካ አማካሪ ሜትር ሎሬንሶ ታዕዛዝና የሕግ አማካሪው ፕሮፌሰር ጋስቶን ዤዝ፣ ተቃውሞአቸውን ለሊቀመንበሩ ቢያመለክቱም የሚያዳምጣቸው አላገኙም።

የፋሽስት ወዳጅ የሆነው የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖልና ቤልጂየካዊው ሊቀመንበር ተስማምተው ለጉባኤው ያቀረቡት ረቂቅ ውሳኔ፣ የኢትዮጵያን ነጻነት ከመኖር ወደ አለመኖር የሚያሸጋግርና የጠላቷን የሙሶሊኒን አቋም የሚያጠነክር ሲሆን፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን ታሪክ ላይ ደግሞ የዘረጉት ጥቁር ጥላ ምን ጊዜም ሲታወስ የሚኖር ነው። " ... በመንግሥታት ማህበር ሕግ በአንቀጽ አሥራ ስድስት መሠረት በጣልያን ላይ ተፈርዶ የነበረው የኢኮኖሚና የፋይናንስ ዕገዳ፣ ከእንግዲህ ወዲህ እንዲቆም የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል መንግሥታት ምኞት ስለሆነ፣ ከዚህ ቀደም የተቋቋመው የሊጉ አስተባባሪ ኮሚቴ አስፈላጊውን እንዲያስፈጽም ተጠይቋል ... " ተብሎ በኮንፌራንሱ ቢሮ ተዘጋጅቶ የቀረበውን ረቂቅ ውሳኔ፣ ጠቅላላው ጉባኤ በዐርባ አራት (44) ድምፅ ብልጫ እንዲያጸድቅላቸው አደረጉ።

ከጉባኤው ተካፋዮች መካከል፣ አብዛኛዎቹ መልዕክተኞች ይህን የቀረበላቸውን ረቂቅ ውሳኔ ሲያጸድቁ በሰጡት መግለጫ፣ ከስምንት ወራት በፊት

ተወስኖ ሥራ ላይ የዋለው " የኢኮኖሚ ዕገዳ " ምንም ዓይነት ውጤት ያልሰጠ መሆኑ ስለተነገረን፣ አሁንም እንዲቀጥል ማድረጉ ምንም ዓይነት ጥቅም የሚያመጣ አለመሆኑን በማሰብ ነው ብለዋል። ይህ የተሰጠው ምክንያት፣ ምን ያህል ከእውነት የራቀ መሆኑንና አስገራሚነቱን፣ በንጉሠ ነገሥቱ ስም ሆነው ደጃዝማች ነሲቡ ዘ አማኔል ለጉባኤው ያስረዱት እንደሚከተለው ነበር።

" ... የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና መልዕክተኞቻቸው፣ ከአንዳንድ የመንግሥታት እንደራሴዎች የተሰጡትን መግለጫዎች ያዳመጡትና፣ በመጨረሻም ጉባኤው አጸደቀው የተባለውን ውሳኔ የተመለከቱት፣ እጅግ በመረረ የኃዘን ስሜት ነው። ከስምንት ወራት በፊት በአጥቂው መንግሥት ላይ የተወሰነውን የኢኮኖሚ ዕገዳ፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል መንግሥታት ሁሉም በተግባር ላይ አለማዋላቸው እየተረጋገጠ፣ የተፈረደውም የኢኮኖሚ ዕገዳ ዝርዝሩ ሲቀርብ፣ የግፈኛውን መንግሥት ጨርሶ የማይጐዳ እንደነበረ በግልጽ እየታወቀ፣ አሁን በመጨረሻው የምታጸድቁት እስከዛሬ የቆየው የኢኮኖሚ ዕገዳ ውጤት ባለማሳየቱ፣ እንዲቆም ያስፈልጋል የሚል ከሆነ፣ ኢትዮጵያን ለማዳን ሌላ ምን እርምጃ ለመውሰድ አቅዳችኋል ? ... ወይም ደግሞ ኢትዮጵያ ነጻነቷ ጠፍቶ ከዓለም ቤተሰብ ብትሰረዝ ግዴለንም ብላችሁ ይሆን ? ለዚህ ተገቢውን ፍርድ ለማግኘት፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የሚከተሉትን ሁለት ረቂቅ ውሳኔዎች ያቀርቡላችኋል።

እነዚህም፡-

፩ኛ/ የመንግሥታት ማህበርን ቃል ኪዳን አፍርሶ፣ እንዲሁም በዓለም ላይ የተደረጉትን ሕጉችና ስምምነቶች ሁሉ ጥሶ፣ ኢትዮጵያን በጦር ኃይል በመያዝ፣ ሕዝቡን በመርዝ ጋዝና በመሣሪያ በመጨረስ ላይ የሚገኘው ግፈኛው የጣልያን መንግሥት፣ ከእንግዲህ ወዲህ " ኢትዮጵያ የኔ ግዛት " ነች ብሎ ያወጣውን ሕገ ወጥ አዋጅ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን እንዲያወግዝና አባል አገሮች ዕውቅና እንዳይሰጡት ውሳኔ እንዲያሳልፍበት፣

፪ኛ/ አንድ የመንግሥታት ማህበር አባል የሆነ አገር ያልተጠበቀ ከባድ ችግር ሲደርስበት፣ የገንዘብና የኢኮኖሚ እርዳታ እንደሚደረግለት፣ በሊጉ አንቀጽ 16 ላይ የተመለከተውን መሠረት በማድረግ ኢትዮጵያ ለነጻነቷ ትግሏን ለመቀጠል እንድትችል፣ አሥር ሚሊዮን ፖውንድ ብድር እንዲሰጣት፣

ሁለቱ የኢትዮጵያ ረቂቅ ውሳኔዎች ያመለክታሉ።

የጉባኤው ሊቀመንበር፣ እነዚህን ሁለት ዕቅዶች ከሊጉ ዋና ጸሐፊ ጋር ከተመካከረበት በኋላ፣ በኢትዮጵያ ግዛት ላይ አሁን ያለው የፋሽስት ይዞታ በይፋ እንዲወገዝና ለወደፊቱም ምንም ዓይነት ዕውቅና እንዳይሰጠው የሚጠይቀውን የመጀመሪያውን ረቂቅ ውሳኔ፣ ለስብሰባው አላቀርብም ብሎ ከለከለ። ቫን ዚላንድ፣ ይህን ከደንብ ውጭ የሆነ እርምጃ የወሰደው፣ ከኢትዮጵያ የተዘጋጀው ረቂት ሐሳብ ለጠቅላላው ጉባኤ ቢቀርብ፣ መልዕክተኞቹ በድምፅ ብልጫ ለማሳለፍ ችግር እንደማይገጥማቸው የተረጋገጠ ስለሆነ፣ ይህ ውሳኔ ዱቼ ሙሶሊኒን በጣም የሚያስቆጣና፣ ለአውሮፓ ሰላም እጅግ አሳሳቢ የሆነ እርምጃ እንዲወስድ፣ የሚገፋፋው ይሆናል በሚል ፍራቻ ነው። በዚህ ምክንያት ቫን ዚላንድ የኢትዮጵያን ጥያቄ አላቀርብም ብሎ ሲጠም፣ የንጉሠ ነገሥቱ የፖለቲካ አማካሪ ሜትር ሎሬንስ፣ ለዮሴፍ አቬኖል በእጃቸው ጽፈው በላኩት አጭር ማስታወሻ ላይ፣ " ...

የምትሠሩት ሁሉ የፋሽስቱን መንግሥት ለማስደሰት ብቻ ከሆነ፣ ለሥራው አመራር እንዲረዳችሁ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጽሕፈት ቤት ከገኔቭ ወደ ሮም እንዲዛወር ለምን ጉባኤውን አትጠይቁም ? ... ኢትዮጵያ ሙሉ ድጋፏን ትሰጣችኋለች ... " ሲሉ የገለጹት ቃል፣ የማሾፍ አነጋገር መስሎ ቢታይም፣ የደረሰው ሁኔታ የኢትዮጵያን መልዕክተኞች ምን ያህል እንዳቆሰላቸው ያመለክታል።

ኢትዮጵያ የሞራል ድጋፍ እንዲሆናት ያዘጋጀችው የሕግ ረቂቅ አለአግባብ ሲሠረዝባት፣ የገንዘብ ብድር እንዲሰጣት የጠየቀችበትም ሁለተኛው ዕቅዷ ለጉባኤው ቀርቦ ድምፅ ሲጠየቅበት፣

- ድጋፍ የሰጠች አንድ አገር ብቻ (ኢትዮጵያ)፣
- ድምፅ አንሰጥም ያሉት አገሮች (አብስቴንሽን) 25፣
- የተቃወሙ አገሮች 23 ሆኑ።

**በዚህ ውጤት ድሉ አሁንም ለፋሽስቶቹ ስለሆነ፣ ለደስታቸው ወሰን አላገኙለትም።**

**እንግዲህ ! የፈረደባት ኢትዮጵያ፣ ለተፈጸመባት በደል አሳዛኝ አቤቱታዋን ያቀረበችላቸው፣ የገኔቩ የመንግሥታት ማህበር ዳኞች፣ ጠላቷን እንደሚቻላቸው አስደስተው ተጠቂዋን ያለ አንዳች እርዳታ እንደ አሰናበቷት ግልጽ ሆኖ ይታያል።**

- **የፋሽስቱ መንግሥት በሊግ ኦፍ ኔሽን ተፈርዶበት የነበረው የኢኮኖሚ ጭቆና እንዲነሣ ተወሰነለት።**
- **የመንግሥታት ማህበርን ሕግ ጥሶ አገሪቷን በጦር ኃይል የወረረው የፋሽስት መንግሥት፣ ይዞታው እንዳይታወቅለት ኢትዮጵያ ያዘጋጀችውን የሕግ ረቂቅ ለጉባኤው ማቅረብ አትችይም ተባለች።**
- **ኢትዮጵያ ነጻነቷን ለማስመለስ ለምታደርገው ትግል፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕግ በሚፈቅደው መሠረት የጠየቀችውን የገንዘብ ብድር ተከለከለች።**

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና መልዕክተኞቻቸው ገኔቭ ሸንጎ ላይ ተገኝተው እንደ ተመለከቱት፣ በዚህ ጉባኤ ላይ የታየው የእንግሊዝና የፈረንሣይ ሚና እጅግ አሳዛኝ ሆኖ አግኝተውታል። ፈረንሣይ ምንም እንኳን፣ ቀደም ሲል በላቫል መንግሥት ጊዜ ኢትዮጵያን ለመክዳቷ በማስረጃ የተያዘባት ቢሆንም፣ አሁን አዲስ የተመረጠው የግራ ክንፍ መንግሥቷ፣ ሌላው ቢቀር በፀረ ፋሽስትነቱ ለዚች ለተበደለች ድሀ አገር የሚገባትን ድጋፍ ሳይሰጣት በመቅረቱ፣ ያልተገረመና ያላዘነ የለም። የታላቋ ብሪታንያ መንግሥትም፣ የሙሶሊኒን ወዳጅነት ለመሳብ፣ የኢኮኖሚው ዕገዳ እንዲነሣ ከአምሳ ሁለቱ እንደራሴዎች መካከል የመጀመሪያው ሐሳብ አቅራቢ ሆኖ መገኘቱ፣ እንኳንስ የኢትዮጵያን መልዕክተኞች፣ የሌሎቹንም አገሮች እጅግ አስገርሟል።

እርግጥ ነው ! በዚህ ዓለም ታሪክ ላይ ተደጋግሞ እንደሚነገረው፣ " ፖለቲካ " እንደ ሃይማኖት ቃል በአንድ ዕምነት ላይ ጸንቶ ለዘለዓለሙ የሚኖር አይደለም። "ፖለቲካ" እንደ አገሩ ጉዳይና እንደሚያስገኘው ጥቅም፣ በየጊዜው ተለዋዋጭ ሆኖ መታየቱ የተለመደ ነው። ይሁን እንጂ፣ በዚህ ሰዓት እንግሊዝና

ፈረንሣይ፣ ከሚያስፈልግ በላይ ከፍርድ ሚዛናቸው ሲንሸራተቱ ፊት ለፊት በመታየታቸው፣ ይቅርታ የሚደረግላቸው አልሆኑም። ማንም ሰው እንደሚያውቀው፣ የእንግሊዝና የፈረንሣይ አቋም፣ " ... ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር ገጥሞ ተጨማሪ ጠላታችን ከሚሆን፣ ኢትዮጵያን መሥዋዕት አድርገን ወገናችን ብናደርገው ይሻላል ... " የሚል ነው። ነገር ግን በሚገባ መታወቅ ያለበት፣ ሙሶሊኒ አጭበርባሪ መሆኑን ነው። ይኸ የማይታመን ሰው፣ ዛሬ የሚፈልገውን ካገኘ በኋላ፣ ነገ እንግሊዝንና ፈረንሣይን ከድቶ ከጠላታቸው ከሂትለር ጋር በመሰለፍ፣ ዋና ጠላታቸው እንደሚሆን የሎንዶንና የፓሪስ መንግሥታት አርቆ ማየትና መጠንቀቅ ነበረባቸው። ቤኒቶ፣ ነገ ጠላታቸው መሆኑ ካልቀረ ደግሞ፣ ዛሬ ኢትዮጵያን መሥዋዕት አድርጎ ከመስጠት፣ ነጻነቷን ለማዳን ቢቆሙላት ዱቼ፣ ነገ ወደ ሂትለር ለመሄድ ያሰበውን ጉዞ፣ ምናልባት ለምን ዛሬውኑ አልጀምርም? ... ይል ይሆናል። ታዲያስ! ቢጀምርስ ? በዚያን ሰዓት ሙሶሊኒና ሂትለር አንድነት ሆነው፣ በእንግሊዝና በፈረንሣይ መንግሥታት ላይ የሚያፈነዱት በጉብ አልነበራቸውም። ሁለቱ ዲክታተሮች ለሎንዶንና ለፓሪስ አሥጊ ለመሆን ቢያንስ የሦስት ዓመታት ዝግጅት ይጠይቃቸው ነበር። ከዚህም በቀር በዚያን ሰዓት፣ የሙሶሊኒና የሂትለር ወዳጅነት ይህን ያህል የሞቀና መሠረት የጨበጠ አልነበረም። ይህንንም ለማመን የሚያስችለው፣ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱን በከፈተ ጊዜ፣ ሂትለር የቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴን መንግሥት በሥውር ጉዳና የጦር መሣሪያ ለመርዳት እርምጃ ወስዶ እንደነበረ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው ሴርጅ ግሩሳር (Serge Groussard) ለተባለው የፈረንሣይ የፊጋሮ (Figaro) ጋዜጠኛ እ.ኤ.አ በ1956 ዓ.ም በሰጡት ኢንተርቪው አስረድተዋል። ስለዚህ፣ እንግሊዝና ፈረንሣይ በነበራቸው ተደማጭነት የሊግ ኦፍ ኔሽን አባሎችን አስተባብረው፣ ለኢትዮጵያ ነጻነት በሙሶሊኒ ላይ የተቃውሞ እርምጃ ወስደውበት ቢሆን ኖሮ፣ በዚያን ሰዓት በዱቼ በኩል የሚገጥማቸው ችግር ከሦስት ዓመታት በኋላ ካደረሰባቸው ብርቱ አደጋ እጅግ ያነሰ ይሆን ነበር።

ነገር ግን ምን ይሆናል ? በዚያን ዘመን፣ ለፈረደባት ኢትዮጵያ የሚያስብላት ወዳጅ አልነበራትም።

ልጆቿ፣ እንደዚያ በመርዝ ጋዝ ሲነዱ፣
እንደዚያ በመትረየስ ሲቆሉ፣
እንደዚያ በመድፍና በታንክ ሲጨፈለቁ፣
እንደዚያ በአካፋና በዶማ ሲወገሩ፣

ግፈኛውን ጠላቷን እንኳንስ በጦር ኃይል የሚወጋላት፣ በፍርድ ሸንጎ ላይ ቆሞ የሚሟገትላት ሳታገኝ ቀረች። ለካስ ! የሠለጠነው ዓለም የዴሞክራሲ አሠራር እንደዚህ ኖሮዋል ? ...

ለድሃው ከመፍረድ፣ ጌታውን ማስተናገድ !




ንጉሠ ነገሥቱ በስደት ሎንዶን ሲገቡ፤ ሕዝቡ ያደረገላቸው አቀባበል፤



ከጃንሆይ በቀኝ ያሉት አቶ ወልደጊዮርጊስ ወ.ዮ ሲሆኑ፤ በግራ ደግሞ
የሚታዩት አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ ናቸው።

# ምዕራፍ ፲፩

## በሊግ ኦፍ ኔሽን የኢትዮጵያ አባልነት ይቀጥላል ? ወይስ ይቋረጣል ?

እ.ኤ.አ ባለፈው ሐምሌ 4 ቀን 1936 ዓ.ም በዓለም ታሪክ ላይ ምንጊዜም አሳዛኝ ሆኖ ሲታሰብ የሚኖረውን ዳኝነት፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን የፈጸመው፣ የፋሽስቱን መንግሥት ለማስደሰትና በወዳጅነቱ ለመጠቀም ነበር። ነገር ግን ቤኒቶ ሙሶሊኒ ይህንን እርዳታ በቂ አድርጐ አልቆጠረውም።

የዓለምን ሕግ ጥሶ የኢትዮጵያን ነፃነት በመግፈፍ፣ አገሪቷን ቅኝ ግዛቱ አድርጌያታለሁ ብሎ ካወጀ በኋላ፣ የፋሽስቱ መሪ የሚከተሉትን ሁለት ጥያቄዎች እንዲፈጸሙለት ጠየቀ። እነዚህም፡- 1ኛ/ ሊግ ኣፍ ኔሽን ኢትዮጵያ የጣልያን ግዛት መሆኗን አውቆ ከማህበሩ አባልነት እንዲሰርዛት፣ 2ኛ/ የመንግሥታት ማህበር አባሎች ሁሉ፣ ቪክቶር አማኑኤል ሳልሣዊ የጣልያንና የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መሆናቸውን አውቀው፣ በፋሽስቱ መንግሥት ዘንድ ለሚመድቧቸው አምባሳደሮች የሹመት ደብዳቤያቸውን በአዲሱ መልክ እንዲያስተካክሉ ለማስደረግ ነበር።

ከእነዚህ ከሁለት ሐሳቦች ውስጥ፣ በመጀመሪያ ደረጃ መወሰን ያለበት፣ በመስከረም 21 ቀን 1936 ዓ.ም በጄኔቭ በሚካሄደው በአሥራ ሰባተኛው የመንግሥታት ማህበር መደበኛው ጠቅላላ ስብሰባ ላይ፣ ኢትዮጵያ መልዕክተኞቿን ልካ መካፈል ትችላለች ? ወይስ አትችልም ? የሚለው ጥያቄ ነበር። የማህበሩ ዋና ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል (Joseph Avenol) ምንም እንኳ በፋሽስታዊ ስሜቱ ኢትዮጵያ እንደሌለች የምትቆጠር ነች ብሎ የሚያምን ቢሆንም፣ የዱቼን ፍላጐት በሥልጣኑ ለመፈጸም ስለማይችል፣ ጉዳዩን ለምክር ቤቱ አቅርቦ ማስወሰን ግዴታ ሆነበት። በዚህ ጊዜ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልዕክተኞቻቸውን አስከትለው በዚህ በመስከረሙ ስብሰባ ላይ ተካፋይ ለመሆን ወደ ጄኔቭ እንደሚመጡ፣ በስደት ከሚኖሩበት ከእንግሊዝ አገር በቴሌግራም አስታወቁ። ሙሶሊኒ ይህንን እንደሰማ፣ ወዲያውኑ ለመንግሥታት ማህበር አንድ ማስጠንቀቂያ ላከ። ኢትዮጵያ ራሷ በጫረችው ጦርነት ድል ሆና በጣልያን ተይዛለች። ንጉሠ ነገሥቱም፣ ቤተሰቦቻቸውንና ገንዘባቸውን ይዘው ከአገር ወጥተዋል። ሕዝቡም የጣልያንን አስተዳደር በደስታ መቀበሉን ስለገለጸ፣ ለነፃነት ተዋጊዎች ነን ብለው ከንጉሥ ኃይለሥላሴ ጋር የተሰለፉት ሁሉ፣ በሰላም እጃቸውን እየሰጡ ከጫካ ወደ ከተማ ተመልሰዋል። በጄኔቭ ዋና መልዕክተኛቸው አድረገው የሾሙትም ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር፣ ለጣልያን መንግሥት ታማኝነቱን ገልጾ ወደ አገሩ ተመልሷል። ስለዚህ፣ ኢትዮጵያ ከእንግዲህ ወዲህ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል መሆኗ የተሰረዘ ስለሆነ፣ በዚህ በመስከረሙ ስብሰባ ላይ መልዕክተኛ ሸማ መላክ አትችልም። ሊግ ኦፍ ኔሽንም፣ ሕዝባቸው ከድቷቸው ከአገራቸው ሸሽተው የወጡትን ንጉሥ የኢትዮጵያ መልዕክተኛ አድረጐ ከተቀበላቸው፣ የጣልያን መንግሥት በስብሰባው የማይካፈል መሆኑ እንዲታወቅለት ያስፈልጋል ሲል፣ ማስጠንቀቂያውን ደመደመ።

ከአንድ ዓመት ወዲህ ፊታውራሪ ተክለሐዋርያትን በመተካት፣ በፓሪስ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትርና በዤኔቭ የመንግሥታት ማህበር ዘንድ ዋና መልዕክተኛ የነበሩት ብላቴን ጌታ ወልደማርያም፣ የመስከረሙ ስብሰባ ከመጀመሩ በፊት ከጣልያን መንግሥት ጋር ተስማምተው ወደ አገራቸው ለመመለስ መወሰናቸው እንደተሰማ፣ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴና አብረዋቸው ባሉት ረዳቶታቸቸው ዘንድ ከፍ ያለ ድንጋጤ ተፈጠረ። ይኸውም፣ በዤኔቭ የተሾሙት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልዕክተኛ የፋሽስትን አስተዳደር ተቀብለው ለጣልያን ገቡ ሲባል፣ የሙሶሊኒ መንግሥት በሚነዛው ፕሮፓጋንዳ ኢትዮጵያን ከሊግ ኦፍ ኔሽን አባልነት ለማስወገድ ይመቸዋል በሚል ሥጋት ነበር።

በዚያን ጊዜ በፓሪስ የኢትዮጵያ ለጋሲዮን አንደኛ ፀሐፊ የነበሩት አክሊሉ ሀብተወልድ፣ (ኋላ ጸሐፊ ትዕዛዝ) በደርግ ዘመን እሥር ቤት ሆነው በጻፉት ማስታወሻ ላይ እንደገለጹት፣ ንጉሠ ነገሥቱ ዤኔቭ ሆነው ብላቴን ጌታ ወልደማርያምን በስልክ በማነጋገር፣ ወደ ጣልያን ለመግባት ያሰብከውን ከመፈጸምህ በፊት፣ በትግላችን ላይ ችግር እንዳይፈጠር፣ በመጀመሪያ ሥራህን በፈቃድህ መተውክን ብታስታውቅ አይሻልም ወይ ? ብለው ጠይቀዋቸው ነበር። የጃንሆይ ሐሳብ፣ ወልደማርያም የኦፊሲየል ሥራቸውን ከለቀቁ በኋላ፣ በግላቸው ለጣልያን አስተዳደር ገብቻለሁ ቢሉ፣ ጠላት የሚጠቀምባቸው ፕሮፓጋንዳ በኢትዮጵያ ላይ ይህን ያህል የሚያስከትለው ጉዳት አይኖርም በሚል አስተያየት ላይ የተመሠረተ ነበር። አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ በማስታወሻቸው እንደጠቀሱት፣ ብላቴን ጌታ ወልደማርያም ለጣልያን ለመግባት የወሰኑበትን ምክንያት ሲያስረዷቸው፣ አንተ በዕድሜህም ወጣት፣ የተማርክ በመሆንህም ሠርተህ መኖር ትችላለህ። እኔ ግን ዕድሜዬ ገፍቷል። በዚህ ላይ ልጆች አሉኝ። ምን ልሁን ትለኛለህ ? ብለዋቸዋል።

በባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩና በአንደኛ ጸሐፊው መካከል ብዙ ውይይትና ክርክር ከተደረገ በኋላ፣ በመጨረሻው ከችግሩ ለመዳን በሚከተሉት ነጥቦች ላይ እርምጃ ለመውሰድ ከስምምነት ደርሰው ነበር።

1ኛ/ ብላቴን ጌታ ወልደ ማርያም ወደ ጣልያን ኤምባሲ ሄደው ዕርቅ ሲጠይቁ፣ ለጓዝ ማንሻና ለመንገድ ስንቅ አምባሳደሩ ቃል የገባላቸውን ገንዘብ እንዲቀበሉ፣

2ኛ/ ገንዘቡን ከተቀበሉ በኋላ ወደ መኖሪያቸው ተመልሰው ታምሚያለሁ ብለው አልጋ እንዲይዙ፣

3ኛ/ የለጋሲዮኑ አንደኛ ጸሐፊ፣ ወዳጅ የሆነ ሐኪም ፈልገው፣ የባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ ሕመም የአእምሮ መታወክ ነው የሚል የሀሰት ሰርቲፊካ እንዲያጽፉ፣

4ኛ/ የሐኪም መረጃ ከተገኘ በኋላ፣ ብላቴን ጌታ ወልደማርያም በደረሰባቸው ሕመም ምክንያት የሚሠሩትን ሁሉ የሚያውቁ አለመሆናቸውን እና የሌጋሲዮኑም ሥራ አንደኛው ጸሐፊ ጉዳይ ፈጻሚ ሆኖ እንዲሠራ ንጉሠ ነገሥቱ መወሰናቸውን ጋዜጣዊ መግለጫ እንዲወጣ፣ ተስማሙ።

እነዚህ ከዚህ በላይ የተዘረዘሩት ሐሳቦች በዚያን ሰዓት ዤኔቭ ለሚገኙት ለኢትዮጵያ መሪ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በስልክ ተነግሯቸው፣ በዚሁ እንዲፈጸም

በደስታ መፍቀዳቸውን አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ በማስታወሻቸው ላይ ገልጸዋል። ነገር ግን፤ በዚህ መልክ የታሰበው ሁሉ ሊፈጸም አልቻለም። ወልደማርያም ፓሪስ ከሚገኘው የጣልያን ኤምባሲ ሄደው፤ አምባሳደሩን ለማነጋገር ቢሞክሩ ሳይቀበላቸው ቀረ። የፋሽስቱ መንግሥት የሚፈልገው፤ የዤኔቩ የሊግ ኦፍ ኔሽን የመስከረም ወር ስብሰባ ከመጀመሩ በፊት፤ ባይሆን ደግሞ ጉባኤው እንደተከፈተ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ከጣልያን ጋር ዕርቅ ማድረጋቸውን የሚያረጋግጠውን ቃለ መሀላ በይፋ እንዲፈጽሙና ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዋና መልዕክተኛቸው ከድቷቸው ብቻቸውን ቀርተዋል ተብሎ በዓለም ላይ ፕሮፓጋንዳ ለመንዛት ነበር። አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ እንደገለጹት፤ ብላቴን ጌታ ወልደማርያም በጣልያን ኤምባሲ አቀባበል ባለመደሰት የሚደርስብኝን ችግርና ፈተና እቀበላለሁ እንጂ፤ ከፋሽስት መንግሥት ጋር አልደራደርም እስከማለት ስለደረሱ፤ ጃንሆይም ዤኔቭ ሆነው ይህን በሰሙ ጊዜ በጣም ተደስተው ነበር። በመካከሉ በሎንዶን ንጉሠ ነገሥቱን በሥራ ይረዱ የነበሩት አቶ ታደሰ መሸሻና አቶ በሻህ ውረድ ሀብተወልድ፤ ፋሽስት በልጆቻቸውና በቤተሰቦቻቸው ላይ የሚነባቸውን ከባድ ችግር ለጃንሆይ አመልክተው፤ ከጣልያን ጋር ዕርቅ ካደረጉ በኋላ፤ ወደ ኢትዮጵያ ሲመለሱ እግረ መንገዳቸውን ፓሪስ ላይ ከብላቴን ጌታ ወልደማርያም ጋር ተገናኝተው የሐሳብ ልውውጥ አደረጉ። እነዚህ ከላይ የተጠቀሱት የንጉሠ ነገሥቱ የቅርብ ረዳቶች የነበሩት ታላላቅ ሰዎች ያጋጠማቸው ችግርና የወሰዱት እርምጃ ከእኔ በምን የተለየ ይሆናል ? በማለት፤ ወልደማርያም ሐሳባቸውን ለውጠው፤ እ.ኤ.አ መስከረም 23 ቀን 1936 ዓ.ም የዤኔቭ ጉባኤ በተከፈተ ማግሥት ጣልያን ኤምባሲ ሄደው ለፋሽስት መንግሥት ታማኝነታቸውን በመግለጽ ወደ አገራቸው ለመመለስ ወሰኑ።

የብላቴን ጌታ ወልደማርያም ለጣልያን መግባት በአውሮፓ፤ በተለይም በጣልያንና በፈረንሣይ ጋዜጦች ላይ በወጣ ማግሥት፤ ንጉሠ ነገሥቱ የሚከተለውን ደብዳቤ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ላኩ።

ሞአ-አንበሳ ዘ-እምነገደ ይሁዳ
እኔ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ
ሥዩመ እግዚአብሔር ንጉሠ ነገሥት ዘ-ኢትዮጵያ
ይድረስ ለክቡር ሙሴ አቬኖል
የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ
ሰላም ለእርስዎ ይሁን፤

በፓሪስ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትርና በመንግሥታት ማህበር ዘንድ ቋሚ መላዕክተኛዬ የነበረውን ብላቴን ጌታ ወልደማርያምን ከሰጠሁት ሥልጣን የሻርኩት መሆኔን ለክቡርነትዎ እገልጻለሁ። በምትኩም በሊግ ኦፍ ኔሽን ዘንድ ቋሚ መላዕክተኛዬ አድርጌ "ሜትር ላውራንስ (ሎሬንስ) ታዕዛዝን" መሾሜን ለክቡርነትዎ አስታውቃለሁ።

ፊርማ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ
ንጉሠ ነገሥት ዘ-ኢትዮጵያ

ይህ የንጉሠ ነገሥቱ ደብዳቤ የተላከው፤ ብላቴን ጌታ ወልደማርያም ጣልያን ኤምባሲ ሄደው መሐላቸውን ከመፈጸማቸው በፊት ቢሆን ኖሮ ምናልባት፤ የተሻለ በሆነ ነበር። ነገር ግን፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዋና



እ.ኤ.አ ከመስከረም 1936 ዓ.ም ጀምሮ ፈረንሣይ በጀርመን እስከተያዘችበት ሰኔ 1940 ዓ.ም ድረስ፣ አክሊሉ ሀብተወልድ በፓሪስ የኢትዮጵያ ለጋሲዮን ሻርገፍ ዳ ፌር ሆነው፣ የኢትዮጵያ ነፃነት አልተነካም እያሉ ይታገሉ ነበር።

*ሥዕሉ የሚያሳየው አክሊሉ ሀብተወልድ ከውጭ አገር ዲፕሎማቶች ጋር ሆነው ነው።*

መልዕክተኛዬን ሽሬዋለሁ ብለው መግለጫ ያወጡት፤ ወልደማርያም የራሳቸውን እርምጃ ከወሰዱና ጉዳዩም በዜና ማሰራጫ ድርጅቶች ከተነዛ በኋላ ስለሆነ፤ የንጉሠ ነገሥቱን የሽረት ማስታወቂያ ጋዜጦቹ ሊገልጹት አልፈለጉም። ይልቁንም በጣም አስገራሚ የሆነው፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ኮሚቴ ላይ የኢትዮጵያን መልዕክተኛ ስለመቀበልና አለመቀበል በደጋፊዎቹና በተቀዋሚዎቹ መካከል ክርክሩ በሚጧጧፍበት ጊዜ፤ የፋሽስት ወገኖች፤ ንጉሠ ነገሥቱ በገኔቭ የነበረው ዋና መልዕክተኛቸው ጭምር ከድቷቸው ብቻቸውን የቀሩ ናቸው በማለት፤ በስብሰባው ላይ ሳይጮሁ መቅረታቸው ነው። የሙሶሊኒ ደጋፊዎች የሆኑት ሁሉ በስብሰባው ላይ እየደጋገሙ የሚያሰሙት ድምፅ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና መንግሥታቸው፤ አዲስ አበባን በሰላም አስረክበው፤ ቤተሰቦቻቸውንና ገንዘባቸውን ይዘው ከአገራቸው ሸሽተው የወጡ ሲሆን፤ በሌላ በኩል ደግሞ፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ የጣልያንን አስተዳደር በደስታ መቀበሉን ሰላማዊ ሰልፍ እያደረገ በማረጋገጥ ላይ ይገኛል። ስለዚህ፤ አሁን ንጉሠ ነገሥቱ ማንን ይዘውና በማን ስም ሆነው ነው ? በሊግ ኦፍ ኔሽን ስብሰባ ላይ መልዕክተኞቼን ይገኙ ካልተካፈልኩ ብለው የሚያስቸግሩት ? ... በማለት ዲስኩራቸውን ሲያስፋፉ፤ የንጉሠ ነገሥቱን ዋና መልዕክተኛ የብላቴን ጌታ ወልደማርያምን ለጣልያን መግባት፤ የማስረጃ ነጥብ አድርገው አልተጠቀሙበትም። ይህ መቼም እግዚአብሔር በተዓምሩ የሸፈነው ጉዳይ ነው በማለት፤ ንጉሠ ነገሥቱና አብረዋቸው የነበሩት ሁሉ ከፍ ያለ እርካታ አግኝተውበታል። ይሁን እንጂ፤ ብላቴን ጌታ ወልደማርያም ከጣልያን ጋር ዕርቅ አድርገው ወደ አገራቸው ወደ ኢትዮጵያ ቢመለሱም፤ በሕይወት በቆዩበት ዘመን ለፋሽስት መንግሥት ያበረከቱት አገልግሎት አለመኖሩ ታውቋል።

ኢትዮጵያን የሚጠላው የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊም፤ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው ፈርመው የላኩለት ደብዳቤ ደርሶት፤ እንኳንስ ብላቴን ጌታ ወልደማርያምን ሽረት ይቅርና፤ የሎሬንሶ ታዕዛዝንም ዋና መልዕክተኛ ሆኖ መሾም፤ የአባል መንግሥታት እንደራሴዎች እንዲያውቁት አላደረገም። ይህንንም ያደረገው፤ ኢትዮጵያ ከመኖር ወደ አለመኖር የተሸጋገረች ስለሆነ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የሚያደርጉትን ሽረት ሆነ ሹመት ለመከታተል ጊዜ የለንም በሚል የዕብሪት መንፈስ መሆኑ ተደርሶበታል። ከዚህም በቀር የክሬደንሻሉ ኮሚቴ ሆነ ከበላይ ያለው ዋና ጉባኤ፤ የኢትዮጵያን መልዕክተኛ እንደማይቀበል ዮሴፍ አቬኖል እርግጠኛ ነበር።

የክሬደንሻሉ ኮሚቴ ጉዳዩን በሚያጠናበት ጊዜ፤ የፋሽስቱ መንግሥት ደጋፊዎች፤ ኢትዮጵያ እኮ መንግሥት የላትም። በጣልያን አስተዳደር ተይዛለች። ስለዚህ፤ ከማን ወኪል ጋር ነው የምንነጋገረው ? ... እያሉ ሲያፌዙ፤ በገኔቭ የጃንሆይ የሕግ አማካሪ ሆኖ የሚያገለግለው ፈረንሣዊው ፕሮፌሰር ዤዝ፤ በብስጭት ተነሳስቶ ተገቢውን መልስ ለመስጠት የጉባኤውን ሊቀመንበር ጠይቆ ነበር። ነገር ግን፤ በዚህ ጉባኤ ላይ ተካፋይ የነበረው የፈረንሣይ መንግሥት መልዕክተኛ፤ አንተ የፈረንሣይ ዜጋ ስለሆንክ፤ የኢትዮጵያ ጉዳይ አይመለከትህም፤ ብሎ ከስብሰባው አዳራሽ እንዲወጣ አስደረገው። ወዲያው፤ ሎሬንሶ ታዕዛዝ ምንም እንኳ አዲሱን የዋና መልዕክተኛነት ሹመታቸውን የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ ገና ያልተቀበለው ቢሆንም፤ ኢትዮጵያ መልስ መስጠት አለባት በማለት ኃይል ቃል ስለአሰሙ፤ ሊቀመንበሩ እያመነታ መድረኩን ፈቀደላቸው። ሜትር ሎሬንሶ በሰጡት መግለጫ፤ የፋሽስት ጦር ከአዲስ አበባ እና ከአንዳንድ ታላላቅ ከተሞች በስተቀር፤ የኢትዮጵያን ግዛት በሙሉ ለመያዝ አለመቻሉንና፤ በየአውራጃዎቹ የተሰማሩትም አርበኞቻችን ጠላትን እያስጨነቁ ጦርነቱን

መቀጠላቸውን፤ ከዚህም በላይ በምዕራብ ኢትዮጵያ ጎሬ ከተማ ላይ የተቋቋመው የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ዋና መምሪያ፤ አስተዳደሩን በሚገባ በማካሄድ ላይ እንደሚገኝ፤ ማስረጃዎቹን ለአባል መንግሥታት ሁሉ ለማቅረብ ዝግጁ ነን ሲሉ አስታወቁ።

በዚህ አኳኋን ኮሚቴው፤ ከኢትዮጵያና ከጣልያን የቀረበውን ሐሳብ ከመረመረ በኋላ፤ ጉዳዩ በዋናው ጉባኤ በድምፅ ብልጫ እንዲወሰን አስተላለፈ። በዚህ መሠረት፤ በስብሰባው ላይ ተካፋይ ሆነው ከተገኙት ከአርባ ዘጠኝ (49) የመንግሥታት መልዕክተኞች መካከል ሠላሣ ዘጠኙ (39) የኢትዮጵያን ጥያቄ ሲደግፉ፤ ተቀዋሚዎች የሆኑት አራት አገሮች፤ ኦስትሪያ፣ ሁንጋሪያ፣ አልባኒያና ኢኳዶር ነበሩ። ድምፅ ባለመስጠት ገለልተኞች ነን ያሉት ስድስቱ አገሮች ደግሞ፤ ቡልጋሪያ፣ ፓናማ፣ ፖርቱጋል፣ ሲያም፣ (ዛሬ ታይላንድ) ስዊትዘርላንድና ቬንዙዌላ መሆናቸው ታወቀ።

በዚህ በተገኘው ውጤት፤ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴና በረዳቶቻቸው ዘንድ ያደረው ደስታ ወሰን አልነበረውም። ይኸውም፤ ኢትዮጵያ ምንም እንኳ በፋሽስት ጦር ኃይል ብትያዝም፤ በዓለም መንግሥታት ዘንድ ነፃነቷ እንደሞተ አልተቆጠረም። ሰላሣ ዘጠኝ መንግሥታት፤ የሙሶሊኒን ሐሳብ አልተቀበሉም በማለት ነበር። ከዚህ በኋላ፤ ንጉሠ ነገሥቱና አብረዋቸው የነበሩት ተከታዮቻቸው፤ ራስ ካሣ ኃይሉ፣ ሐኪም ወርቅነህና አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከዠኔቭ ወደ ሎንዶን ሲመለሱ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ዘንድ አዲስ የተሾሙት ዋና መልዕክተኛ ሜትር ላውራንስ (ሎሬንሶ) ታዕዛዝ በጉባኤው ላይ ተካፋይ በመሆን ሥራቸውን ቀጠሉ።

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ እንደታየው፤ ኢትዮጵያ የአባልነት ቦታዋን ይዛ፤ **አለሁ! አልሞትኩም!** በማለት ድምጿን ለዓለም ለማሰማት ካልሆነ በስተቀር፤ ነፃነቷን ከፋሽስት ለማላቀቅ ሊግ ኦፍ ኔሽን አንዳች የሚሰጣት እርዳታ እንደሌለ ለማንም ግልጽ ነው። ከዓለም ሕግ ውጪ አንድ የማህበሩ አባል የሆነ መንግሥት፤ ሌላውን አባል አገር በጥጋብ ተነስቶ በጦር ኃይል ነፃነቱን ሲገፍና ቅኝ ግዛቴ አድርጌዋለሁ ብሎ ሲያውጅ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን የተመሠረተበትን ዓላማና ግዳጅ መፈጸም እንዳልቻለ፤ በዚህ በኢትዮጵያ ጉዳይ በሚገባ አስመስክሯል። ፍርድ የጎደለባት ኢትዮጵያ የተቀበለችው ግፍ ብዙ ነው።

- ነፃነቷን ለመከላከል እንድትችል፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን ደንብ የሚፈቅደውን የገንዘብ ብድር ብትጠይቅ፤ ያለ አንዳች ምክንያት ተከልክላለች፤

- ባላት አቅም የመከላከያ መሣሪያ ለመግዛት እንዲፈቀድላት ለታላላቆቹ አገሮች ብታመለክት፤ አይቻልም ተብላለች፤

- ቀደም ሲል የገዛቻቸውም የጦር መሣሪያዎች፤ ዕድሜ ለፈረንሣይ መንግሥት፤ ጠላቷ ፋሽስት እንዲጠቀምበት ጂቡቲ ላይ ተነጥቃለች፤

- እስካሁን ከደረሰባት ከዚህ ሁሉ በደል በላይ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል ሆና መቆየቷን ጠላቷ የፋሽስት መንግሥት ስለማይፈልግ፤ በምን አኳኋን ከማህበሩ ለማስወጣት እንዲቻል፤ ልዩ ልዩ ተንኮል ሲጠመድባት ይታያል፤

የኢትዮጵያ ሕዝብ፣ ከወደቀበት ግፍና መከራ የሚላቀቅበትን መንገድ እንዲከፍትለት፣ ዕምነቱን በፈጣሪው ላይ ጥሎ ሌት ተቀን ቢፀልይም፣ በየሜካውና በየፈረፈሩ፣ በየበረሃውና በዱር በገደሉ፣ ጠላቱን እየወጋ መስዋዕትነትን ከመቀበል አላቋረጠም። ንጉሠ ነገሥቱም፣ ሊግ ኦፍ ኔሽንና አባሎቹ መንግሥታት፣ ለዚች ለተበደለች ደሐ አገር የሚሰጡትን ፍርድ እግዚአብሔርና ታሪክ ይመለከቱታል ብለው፣ የወረወሩት ትንቢት ደርሶ የማየት ዕድል እንደሚገጥማቸው ተስፋቸውን ሳይቆርጡ፣ ኢትዮጵያ ከማህበሩ አባልነት እንዳትወገድ ያደረጉት ትግል ቀላል አለመሆኑን ለመገንዘብ አያዳግትም።

በዚህ ምዕራፍ መግቢያ ላይ እንደተጠቀሰው፣ የሙሶሊኒ ፍላጐት፣ ከእንግዲህ ወዲህ በጣልያን ፋሽስታዊና ንጉሣዊ መንግሥት ዘንድ አዲስ የሚሾሙት የየአገሩ አምባሳደሮችና ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሮች፣ በሹመት ደብዳቤያቸው ላይ የሚጻፈው አድራሻ፣

ለግርማዊ ቪክቶር አማኑኤል ሳልሣዊ
የጣልያን ንጉሥና የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት
ሮም-ኩሪናል ተብሎ እንዲገለጽ ማሳሰቢያ ተሰጠ።

ከትልልቆቹ መንግሥታት መካከል አጋጣሚ ሆኖ በሮም የፈረንሣይ አምባሳደር የነበረው ሙሴ ደ.ሻምብረን (M.De Chambrun) የሥራ ጊዜውን ፈጽሞ ወደ አገሩ ለመመለስ፣ ጥቅምት 16 ቀን 1936 ዓ.ም የፋሽስቱን መሪ ለመሰናበት ሲቀርብ፣ ዱቼ እንድ ማሳሰቢያ ሰጠው። " ... ወደፊት አንተን የሚተካው አዲሱ የፈረንሣይ አምባሳደር፣ የጣልያን ንጉሥ የኢትዮጵያም ንጉሠ ነገሥት መሆኑን የሚገልጽ የሹመት ደብዳቤ ይዞ ካልቀረበ አንቀበለውም ... " አለው። አምባሳደሩ ደንግጦ ለመከራከር ሞከረ። የፈረንሣይ መንግሥት በሊግ ኦፍ ኔሽን ከሚሰጠው ውሳኔ ውጭ ለብቻው ተነጥሎ፣ ጣልያን የኢትዮጵያን ግዛት የራሷ አድርጋ መያዟን በይፋ ለማወቅ ከባድ ችግር መሆኑን አስረዳ። ሙሶሊኒ ይህን ምክንያት አልተቀበለም። " ... ችግራችሁ ይህ ከሆነ፣ የተሻለው መንገድ አንተን እዚሁ በአምባሳደርነት ሥራህ እንድትቀጥል ማድረግ ነው። አንተ፣ አዲሲቷ ጣልያን አዲሱን ኢምፓየር (Empire) ከመመሥረቷ በፊት የተሾምክ ስለሆነ፣ አዲስ የሹመት ደብዳቤ አቅርብ አንልህም። ከዚህ በላይ (በፌዝ አነጋገር) ሁለት ሰይጣኖች በሚገባ ከተዋወቁና አብረው ከኖሩ፣ ከጊዜ ብዛት ተዓምር መሥራት ይችላሉ ይባላል። እንደዚሁም አንተም እኛን፣ እኛም አንተን በማወቅ ተቻችለን ብዙ ዓመታት ስለኖርን፣ ከእንግዲህ ወዲህ ለጋራ ጥቅማችን በመሥራት ብዙ ፍሬዎች እናመርት ይሆናል ብዬ አስባለሁ... " አለው። አምባሳደሩም መልስ ለመስጠት አልዘገየም። " ... እኔ እንደማውቀው፣ ሁለት አጋንንቶች ከጊዜ ብዛት ተስማምተው ለመኖር የሚችሉት፣ በየግላቸው እንደኛው በአንዱ ጉዳይ እንዳይገባ በመከባበር እንጂ፣ ለጋራ ጥቅማቸው አብረው በመሥራት አይደለም ... " አለ።

አምባሳደር ደ. ሻምብረን የሙሶሊኒን ውሳኔ በአስቸኳይ ለአገሩ መንግሥት አስታወቀ።

የፈረንሣይ የግራ ክንፍ መንግሥት መሪ የሆነው ሌዎን ብሉም (Leon Blum) በጣም ተቸገረ። በዚያን ሰዓት ኢትዮጵያ የጣልያን ሆናለች ብሎ በይፋ ለማስታወቅ የሚቻለው አልሆነም። በሌላ በኩል ደግሞ ከሙሶሊኒ ጋር መቃቃርን አልፈለገም። በተጨማሪም፣ በኦፊሲየል ወደ አገርህ ተመለስ ብሎ የጠራውን አምባሳደር፣ መልሶ እዚያው እንዲቆይ ማድረግ፣ የደካማነት መንፈስ መሆኑ ተሰማው። ሌዎን ብሉም

ምን ማድረግ እንደሚሻለው ሲያወጣና ሲያወርድ፤ የሙሶሊኒ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ኮምት ቺያኖ (Comte Ciano) በላከለት ልዩ መልዕክት፤ " ... የፈረንሣይ መንግሥት፤ ቪክቶር አማኑኤል ሳልሣዊ የጣልያን ንጉሥና የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መሆናቸውን ለማወቅ ከተቸገረ፤ አዲስ አምባሳደር በመሾም ፋንታ ኤምባሲውን በአንድ ጉዳይ ፈጻሚ (Charge D'Affaires) ሊያቆየው ይችላል ... " የሚል ሐሳብ ሰጠው። ምንም እንኳ በሁለት ታላላቅ አገሮች መካከል በጉዳይ ፈጻሚ ደረጃ የሚካሄድ የዲፕሎማቲክ ግንኙነት አጥጋቢ ሊሆን ባይችልም፤ ሌዎን ብሉም የቺያኖን ሐሳብ ተቀብሎ መፈጸም የሚሻለው ሆነ። እንግሊዞችም፤ ሙሶሊኒ በፈረንሣይ ላይ የፈጠረው ችግር ለእነሱም ስለማይቀርላቸው፤ በሮም ያለው አምባሳደራቸው ሰር ኤሪክ ድሩሞን (Sir Erik Drummond) በሥራው ላይ እንዲቆይ አደረጉ። ታላላቆቹ አገሮች እንግሊዝና ፈረንሣይ፤ ከዚህ በላይ በተገለጸው አኳኋን ሙሶሊኒ ከፈጠረባቸው ችግር ለማምለጥ ጊዜያዊ መፍትሔ ሲያገኙ፤ ከሌሎቹ የአውሮፓና የእስያ መንግሥታት መካከል አብዛኛዎቹ፤ የፋሽስቱን መሪ ለማስደሰት የየአምባሳደራቸውን የሹመት ደብዳቤ አጻጻፍ ማስተካከል ብቻ ሳይሆን፤ ኢትዮጵያም የጣልያን ግዛት መሆኗን በይፋ ለማወቅ ሲጣደፉ ታይተዋል።

በሊግ ኦፍ ኔሽን በተደረጉት ስብሰባዎች ሁሉ የፋሽስት ደጋፊነታቸውን በግልጽ ሲያሳውቁ የቆዩት የኦስትሪያና የሀንጋሪያ መንግሥታት በህዳር ወር 1936 ዓ.ም በኢትዮጵያ ላይ የሙሶሊኒን ይዞታ እናውቃለን ለማለት ከአውሮፓ አገሮች መካከል የመጀመሪያዎቹ ሆነው ብቅ አሉ። በዚህ ጊዜ እነዚህ አገሮች የመንግሥታት ማህበርን ቃል ኪዳን በማፍረስና የኢንተርናሽናል ሕግን በመጣስ በወሰዱት እርምጃ፤ ወንጀል እንደፈጸሙ ሊቆጠርባቸው ይገባል በማለት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለሊግ ኦፍ ኔሽን አቤቱታ አቅርበው ነበር። ነገር ግን፤ የመንግሥታት ማህበር በኢትዮጵያ ላይ የጣልያንን ይዞታ አባል አገሮች ሁሉ ማወቅ የለባቸውም የሚል ውሳኔ ስላልሰጠ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ያቀረቡትን ተቃውሞ የሚያዳምጥ አልተገኘም። ከኦስትሪያና ከሀንጋሪያ መንግሥታት ቀጥሎ ንጉሠ ነገሥቱ ወዳጆቼና ጨዎች ናቸው ብለው የሚተማመኑባቸው የቤልጂክና የሆላንድ፣ የስዊድንና የዳንማርክ ነገሥታቶች እንዲሁም የሉክሳምቡርግ ዱቼና የፊላንድ ፕሬዚዳንት በአንድ ሰሞን ውስጥ እያከታተሉ በኢትዮጵያ ላይ ባለሥልጣን የሆነውን የሙሶሊኒን ይዞታ አወቁለት። ንጉሠ ነገሥቱን ከእነዚህ አገሮች ቀጥሎ በይበልጥ ያሳዘናቸው፤ የስዊስ ኮንፌዴሬሽን መንግሥት የወሰደው እርምጃ ነበር።

በዚህ ምዕራፍ ላይ እንደተገለጸው፤ እ.ኤ.አ መስከረም 23 ቀን 1936 ዓ.ም ኢትዮጵያ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባልነቷ ተከብሮ መልዕክተኛዋ ወንበሩን እንዲይዝ ከተወሰነ በኋላ፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴና የረዳቶቻቸው ፍላጐት፤ ለአገራችን ነፃነት ለመከራከርም ሆነ አቤቱታችንን ለመቀጠል፤ ንጉሠ ነገሥቱ መኖሪያቸውን ከእንግሊዝ አገር ይልቅ ወደ ዤኔቭ ቢዛውሩ ይሻላል የሚል ነበር። በማናቸውም የዓለም የፖለቲካ ጉዳይ ያለኝ አቅዋም ገለልተኛነትን (ኒውትራል) አጥብቆ የሚከተል ነው የሚለውና ለትክክለኛ ፍርድ ታጋይ መንግሥት ነው እየተባለ ዝና ሲሰጠው የኖረው የስዊስ ኮንፌዴሬሽን መንግሥት፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የመኖሪያ ፈቃድ እንዲሰጣቸው ያቀረቡለትን ማመልከቻ አልቀበልም ብሎ መለሰባቸው። የስዊስ መንግሥት ይህንን ውሣኔ ባስታወቀ ጊዜ የሰጠው ምክንያት፣ የፋሽስት መንግሥት ንጉሠ ነገሥቱን በጥብቅ ስለሚከታተላቸው፤ በተለይ ለፀጥታው አጠባበቅ ከባድ ችግር ይፈጥርብናል የሚል ነበር። ይህ ሁሉ ሰበብ ፍለጋ እንጂ በቂ ምክንያት እንዳልነበረ ብዙዎቹ የፖለቲካ ታዛቢዎች አስተያየት ሰጥተውበታል። በዚያን ጊዜ የስዊስ መንግሥት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የነበረው ሙሴ ጁሴፔ ሞታ (Guseppe Motta) የጣልያን ተወላጅና የፋሽስቱም መንግሥት

አድናቂና ወዳጅ ነኝ ባይ በመሆኑ፣ ከግል ስሜቱ ጋር አጣምሮ በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ላይ የወሰደው አሳዛኝ እርምጃ ስዊሶቹን ሁልጊዜ ሲያሳፍራቸው የሚኖር ነው። የሞታ ፋሽስታዊ አገልጋይነት በዚህ ብቻ አልቆመም። የ1936 ዓ.ም ከመፈጸሙ በፊት፣ ይኸው ከዓለም ፖለቲካ "ኒውትራል" እየተባለ የሚጠራው የስዊስ መንግሥት በኢትዮጵያ የሙሶሊኒን ይዞታ በይፋ ካወቁት የፋሽስት ወዳጆች ከሆኑት መንግሥታት መካከል አንዱ ሆኖ ተገኘ። በዚህ አኳኋን ስዊሶች እንደወሰዱት እርምጃ ሌሎቹም አገሮች የፋሽስት መንግሥት የኢትዮጵያን ነፃነት መግፈፉን እያጸደቁለት ሄዱ። እንደ እውነቱ ከሆነ በዚያ በአገራችን ላይ በወደቀው የመከራ ዘመን ለኢትዮጵያ ነፃነት ከተቆረቆሩት ይልቅ የፋሽስት ወዳጆች በመሆን የሙሶሊኒን ይዞታ ያወቁት አገሮች ቁጥራቸው ምን ያህል በርካታ መሆኑን ማየት እጅግ አሳዛኝ ይሆናል። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ ብለው በሰየሙት የታሪክ ማስታወሻቸው ላይ እንደገለጹት፣ እስከ መጨረሻው ድረስ በኢትዮጵያ ላይ የፋሽስትን ይዞታ አናውቅም በማለት ባመኑበት ፀንተው የቆዩት አገሮች፣ ቁጥራቸው ከአምስት አልበለጠም። እነዚህም፣ ዩናይትድ ስቴትስ፣ የሶቪየት ሕብረትና ቻይና፣ ሜክሲኮና ኒውዚላንድ ናቸው።

እንግዲህ ታሪኩ ባጭሩ በትክክል እንደአሳየን፣ የፈረንጆቹ የ1936 ዓ.ም ለኢትዮጵያ የሚበድላትን እንጂ፣ የሚረዳትን ነገር አላስገኘላትም።

- በግንቦት 5 ቀን የፋሽስት ጦር አዲስ አበባን ያዘ።

- በሐምሌ 30 ቀን የጄኔቩ የመንግሥታት ማህበር ሸንጎ፣ በአጥቂው በፋሽስት መንግሥት ላይ የተወሰደው የኤኮኖሚ ዕገዳ እንዲሰረዝ፣ ታሪካዊውን ሕገወጥ ፍርድ ሰጠ።

- በመስከረም 23 ቀን በሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ስብሰባ ላይ ኢትዮጵያ መልዕክተኛዋን ይዛ እንዳትቀርብ ዕገዳ ለማድረግ ሙከራ ተደረገ።

- በኅዳር ወር አጋማሽ ላይ፣ ከአዲስ አበባ ተዛውሮ ጉሬ ከተማ ላይ የተቋቋመው የኢትዮጵያ መንግሥት፣ በጠላት ጦር ተበትኖ ሥራውን በጠቅላይ ሚኒስትርነት ይመሩ የነበሩት ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ በፋሽስቶች ተማረኩ። ከዚህ በኋላ ብዙዎቹ ታላላቅ መኳንንቶችና የጦር መሪዎች እየታደኑ በግፍ ሲገደሉ፣ ብዙዎቹም ተስፋ በመቁረጥ እጃቸውን ለጠላት እየሰጡ ወደ አገራቸው ተመለሱ። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም ከጥቂቶች ታማኞቻቸው ጋር መራራውን የስደት ሕይወት በእንግሊዝ አገር ሲጀምሩ፣ አውሮፓ ወደ ሁለተኛ የዓለም ጦርነት ጉዞውን ጀመረ። እንግዲህ ! ምን ይሆን የኢትዮጵያ የወደፊት* ዕድል?

* በሊግ ኦፍ ኔሽን ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ የተካሄደውን ዳኝነትና ውሣኔ በጥልቀት ለመረዳት፣ እ.አ.አ ከጥቅምት 1935 ዓ.ም እስከ ሐምሌ 1936 ዓ.ም ድረስ ያለውን፣ "Societé Des nations Journal Officiel" ላይ በዝርዝር በየቀኑ የወጣውን ፕሮሲቬርባል መመልከት ይበቃል።

# ምዕራፍ ፲፮

## የቫቲካን አቋም በኢትዮጵያ ጉዳይ

(በ "Archivo Segreto Vaticano" ደራሲው ያደረገው የምርምር ውጤት)

እ.ኤ.አ በ1935 ዓ.ም የፋሽስቱ መንግሥት መሪ ቤኒቶ ሙሶሊኒ የጦር ኃይሉን አዘጋጅቶ ኢትዮጵያን ሲወር፣ በዚያን ጊዜ የነበሩት የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ካቶሊካዊት ቤተክርስቲያን መሪ ፒዮስ 11ኛ፣ ከዲክታተሩ ዱቼ ጋር ተባብረው ነበር የሚል ዜና በአገራችን እስከዛሬ ድረስ ሲነገር ቆይቷል። ይኸውም፣

1ኛ/ በኢትዮጵያ ላይ የሚደረገው ጦርነት የተቀደሰ ዘመቻ ነው በማለት፣ የሮማው ፓፓ ለጦርነቱ የሚላኩትን ሦስት መቶ ሺህ ወታደሮች ቡራኬ ሰጥተው አሰናብተዋል።

2ኛ/ መድፎቹንና ታንኮቹን ባርከዋል።

3ኛ/ የፋሽስት ጣልያን በኢትዮጵያ ላይ የወሰደችው እርምጃ ትክክለኛ የሆነ የፍርድ ሥራ ነው በማለት፣ የቤተክህነት አባሎችና ምዕመናኑ፣ ከወርቅ የተሠሩ የአንገትና የጣት ጌጦቻቸውን እያወለቁ ለሙሶሊኒ መንግሥት እርዳታ እንዲያስገቡ፣ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሱ ሰበካውን አካሂደው ጥሩ ውጤት አስገኝተዋል፣ የሚል ነው።

የዚህ መጽሐፍ ደራሲ በሮም የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አምባሳደር በነበረበት ዘመን ከተከታተለውና ከሚያውቀው ሌላ፣ በኢትዮጵያ ጉዳይ የቫቲካን ትክክለኛ አቋም እንዴት እንደነበረ በጥልቀት ለመረዳት እ.ኤ.አ ከጥቅምት 18 ቀን እስከ ኅዳር 10 ቀን 2010 ዓ.ም ድረስ ለሦስት ሳምንታት በቫቲካን ሰንብቶ፣ በምሥጢር ተይዘው ለብዙ ዓመታት የኖሩትን ዋና ዋና ሰነዶች በማጥናት፣ ያገኛቸውን መረጃዎች ለአንባቢዎቹ እንደሚከተለው ያቀርባል።

እ.ኤ.አ በታህሣሥ 1934 ዓ.ም ሙሶሊኒ ለጠቡ መጫሪያ ያዘጋጀው የወልወል ግጭት ከፈነዳበት ቀን ጀምሮ፣ የዲክታተሩ ዋና ዓላማ ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ወግቶ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ መሆኑን በመላው የጣልያን ሕዝብና በአውሮፓ መንግሥታት ዘንድ ግልጽ ሆኖ መታየቱ የሚያጠራጥር አልነበረም። በቫቲካን መሪዎች ዘንድ ግን፣ ሙሶሊኒ የንግሥተ ሳባን አገር ለመውረር በእርግጥ መወሰኑንና መዘጋጀቱን አምነው ክትትል ማድረግ የጀመሩት፣ የጣልያን ጦር የኢትዮጵያን ወሰን ከመጣሱ ከሦስት ወር በፊት እ.ኤ.አ በሐምሌ 1935 ዓ.ም ነው። በዚያን ዘመን በቫቲካን የፈረንሣይና የእንግሊዝ አምባሳደሮች የነበሩት ሙሴ ሻርል ሩ (Charles Roux) እና ሰር ዊንግፊልድ (Sir Wingfield) ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሱ ፒዮስ 11ኛ ተቀብለው ሲያነጋግሯቸው፣ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ ያቀደውን ጦርነት አለመደገፋቸውን እንደገለጹላቸው በየማስታወሻቸው አስፍረውታል። የፈረንሣይ አምባሳደር ለመንግሥቱ ባስተላለፈው ራፖር፣ ሊቀጳጳሱ ፒዮስ 11ኛ የፋሽስቱ መንግሥት ኢትዮጵያን ለመውረር ያደረገው

ዕቅድ ምን ያህል እንደአሳሰባቸውና ከፍተኛ ሥጋት እንደአሳደረባቸው አጠንክረው ነግረውኛል ሲል፤ የእንግሊዝ አምባሳደር ደግሞ በበኩሉ፤ የሙሶሊኒን ዓላማ ለማስለወጥ ቅድስት መንበረ ጴጥሮስ ምንም ዓይነት አቅም እንደሌላት ያለባቸውን ችግር ተንትነው ገልጸውልኛል ብሏል። ሆኖም፤ በዚያን ጊዜ ሊቀጳጳሱ ፒዮስ 11ኛ፤ ጉዳዩን ወደ ሰላማዊ ጉዳና በመምራት አንዳንድ እርምጃዎች ለመውሰድ መሞከራቸውን የሚያመለክቱ መረጃዎች ተገኝተዋል።

በመጀመሪያ ያደረጉት ሙከራ፤ ለእንግሊዝ ንጉሥ ጆርጅ ፭ኛ ልዩ መልዕክት በመላክ፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የሰላም ንግግር ለመክፈት፤ ንጉሡ እና ፒዮስ 11ኛ በሕብረት ምን ቢያደርጉ እንደሚሻል አስተያየትና ምክር መጠየቅ ነበር።

ይህንን የፒዮስ 11ኛን ልዩ መልዕክት ለንጉሥ ጆርጅ 5ኛ በእጃቸው እንዲያደርሱ በቫቲካን የተሠየሙት ካርዲናል አርቱር ሄንስሌይ (Arthur Hinsley) የዌስት ሚኒስቴር የካቶሊክ ሊቀ ጳጳስ ነበሩ። እሳቸውም ከመንበረ ጴጥሮስ ቅዱስ መሪ የተላከውን ልዩ መልዕክት ለንጉሡ ለማቅረብ የዊንሰርን (Windsor) ቤተመንግሥት ቀጠሮ ሲጠይቁ፤ ጉዳያቸውን በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር በኩል ማመልከት እንደሚገባቸው ተነገራቸው። በዚህ ጊዜ በምሥጢር የተዘጋጀው ጉዳይ አፈትልኮ ከጋዜጠኞች ጆሮ ስለደረሰ፤ " ... የእንግሊዙ ንጉሥ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረውን ጠብ በሰላም ጉዳና ለመፍታት እንዲቻል፤ የሮማው ፓፓ የላኩላቸውን መልዕክት፤ ጉዳዩ በሚመለከተው በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር በኩል እንጂ፤ በቀጥታ ከቫቲካን እንደራሴ መቀበል አልችልም ብለው መለሱት ... " የሚል ትችት ተሰጠበት።

በዚህ መጽሐፍ በክፍል 2 በምዕራፍ 6 ላይ ተዘርዝሮ እንደቀረበው፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት በሊግ ኦፍ ኔሽን ስም ሆነው ሙሶሊኒ ጦርነቱን ሰርዞ፤ ከኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ አንዳንዶቹን አውራጃዎች መርጦ በመውሰድ፤ ኢኮኖሚውን በፈለገው ዓይነት ለማልማት እንዲችልና በተጨማሪም በአገሪቱ የውጭ ፖለቲካ አመራር ሥልጣን እንዲኖረው ያቀረቡለትን ሐሳብ፤ በነሐሴ 18 ቀን 1935 ዓ.ም አልቀበልም ብሎ የጥጋብ መልስ ሲሰጥ፤ ፒዮስ 11ኛ ከፍ ያለ ጭንቀት አደረባቸው። ይህም ሥጋት፤ የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ በሚያደርገው ጦርነት የብዙ ንጹሐን ደም በከንቱ የሚፈስ ከመሆኑም በላይ፤ መዘዙ ለአውሮፓም ሕዝብ የማይቀርለት ይሆናል በሚል አስተሳሰብ እንደተመሠረተ ይነገራል። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ፤ በቫቲካን በኩል ምን ማድረግ እንደሚቻል፤ ወይም ደግሞ ምን ዓይነት አቋም መውሰድ እንደሚገባ ሲያስቡበት ከሰነበቱ በኋላ፤ ፒዮስ 11ኛ ነሐሴ 27 ቀን 1935 ዓ.ም አስተያየታቸውንና ስሜታቸውን የሚገልጹበት አንድ መንገድ ፈጠሩ። ይኸውም፤ በዚህ በበጋው ወራት ከሐያ ሰባት ልዩ ልዩ አገሮች የተውጣጡ ሁለት ሺህ የሚሆኑ ነርሶች በሮማ የሚያደርጉትን ታላቅ ጉባኤ ከፈጸሙ በኋላ፤ የርዕሰ ሊቃነ ጳጳሱን ቡራኬ ለመቀበል በመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ዙፋን በቀረቡበት ዕለት ነበር።

ፒዮስ 11ኛ እነዚህን በብዙ መቶ የሚቆጠሩትን የዓለም ነርሶች ሲቀበሉ፤ የቅዱስነታቸው ረዳቶች ያዘጋጁላቸውን የቡራኬ ቃል ካነበቡ በኋላ፤ ማንም ያልጠበቀውንና ያላሰበውን ጉዳይ በቃላቸው በመጨመር፤ የሙሶሊኒ መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ስለአቀደው ጦርነት አስተያየታቸውን ገለጹ።



"... ዛሬ በጣልያን መንግሥት የሚዘጋጀው ጦርነት ዓላማው ግዛትን ለማስፋፋት ከሆነ፤ በማያጠራጥር መንገድ ፍትሐዊ አይደለም። ይህም ከሆነ አሳዛኝነቱን ለመግለጽ ቃላት የማይገኝለት አስከፊ ነገር ነው"

እንደሚታወቀው፣ የፋሽስቱ መንግሥት ለአገር ውስጥና ለውጭው ዓለም በሚነዛው ፕሮፓጋንዳ፣ ኢትዮጵያን ለመውረር የሚዘጋጅበት ምክንያት፣

1ኛ/ ኢትዮጵያ በሱማሌና በኤርትራ በኩል ያሉንን ወሰኖቻችንን እየጣሰች በየጊዜው በሕዝቦቻችን ላይ የምታደርስብንን አደጋ ለምንጊዜውም ለማቆም ሲሆን፣

2ኛ/ ከአውሮፓ አገሮች መካከል እንግሊዝና ፈረንሣይ በአፍሪካ ውስጥ ሰፊ ግዛቶች ይዘው አገሩን እያለሙ ሲጠቀሙ፣ ቁጥሩ 43 ሚሊዮን የደረሰው የጣልያን ሕዝብም፣ በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ምንም ሳይሠራበት ተንጣሎ የሚገኘውን ብዙ መሬት ማልማትና መጠቀም ትክክለኛ መብታችን መሆኑ መታወቅ አለበት የሚል ነው።

የሮማ ርዕሰ ጳጳሳት ፒዮስ 11ኛም አስተያየታቸውን የገለጹት እነዚህን የሙሶሊኒን ሁለት መሠረታዊ ምክንያቶች ተመርኩዘው ነበር።

" ... የአገርን ድንበር ለመከላከል ከውጭ ጠላት ጋር የሚደረግ ጦርነትና ግዛትን ለማስፋፋት የሚከናወን የወራሪ ጦርነት፣ ልዩነቱ እጅግ ሰፊ ነው። ዛሬ የሚዘጋጀው ጦርነት ዓላማው ግዛትን ለማስፋፋት ከሆነ፣ በማያጠራጥር መንገድ ፍትሐዊ አይደለም። ይህ ከሆነ ደግሞ አሳዛኝነቱን ለመግለጽ ቃላት የማይገኙለት እስከፊ ነገር ነው። .... የሕዝቡ ቁጥር በየቀኑ እየጨመረ ለሚሄደው አገር ተጨማሪ ግዛት ማግኘት ያስፈልጋል ከተባለ፣ እንዲሁም በግዛት ወሰን ላይ የሚደርሰውን አደጋ መከላከል ግዴታ ከሆነ፣ ሁለቱም ምክንያቶች በሰላማዊ ጉዳና መፍትሔ ሊያገኙ ይችላሉ ብለን ስለምናስብ፣ ሌላ አማራጭ ያለው ምኞት የለንም። በዘመናችን ፍትሐዊ ያልሆነ ጦርነት ይመጣል ብለን ማሰብ ይሳነናል። እንደዚሁም ይኸ ይደርሳል ብለን መገመትም ስለማንችል፣ ሐሳቡን አውጥተን አውርደን ውድቅ አድርገነዋል። ፍትሐዊ ባልሆነ ጦርነት አናምንም። ለማመንም ፈቃደኞች አይደለንም። ... የሕዝቦችን እውነተኛ ደስታና ማሕበራዊ ፍትሐዊነት ለማሟላት የሚያስፈልገውን ሁሉ በሚገነዘቡት አስተዋይ መሪዎች ላይ፣ የእግዚአብሔር ቸርነት እንዲታከልበት እንጸልያለን። የሰዎችን ብሶት እየቀሰቀሱ፣ ሁኔታዎች በየቀኑ እንዲባባሱ ለሚያደርጉት ወገኖች ሳይሆን፣ ለእውነተኛው ሰብአዊ መንፈስና በጐ ዓላማ ቆመው፣ ይህን ከፊታችን የተደቀነውን ጦርነት ለማስወገድ የተቻላቸውን ሁሉ ለሚያደርጉት ሰዎች፣ ቸሩ አምላክ ድካማቸውንና ጥረታቸውን እንዲባርክላቸው ልመናችንን እያቀረብን፣ እናንተም ውድ ልጆቼ በጸሎታችሁ እንዳትለዩ እንማጠናችኋለን ... " *

ከዚህ በላይ የቀረበው የፒዮስ 11ኛ አስተያየት፣ በዓለም የመገናኛ ዘዴዎች በሰፊው ሲወራ፣ በዚያን ሰዓት በፓሪስ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር የነበሩት ለንጉሠ ነገሥቱ በላኩት ቴሌግራም፣ " ... በመንግሥታት ግንኙነቶች መካከል የሚፈጠር ማናቸውም አለመግባባት ወይም ጠብ፣ በሰላም መንገድ መፈታት ያለበት መሆኑን የሮማው ፓፓ ፒዮስ ፲፩ኛ በጥብቅ ካሳሰቡ በኋላ፣ በተለይም ለግዛት ማስፋፊያ የሚደረግ ጦርነት ፍትሐዊ ባለመሆኑ የማይደገፉት መሆናቸውን አስታውቀዋል ... " ሲሉ አመለከቱ። ጃንሆይ

* ፒዮስ 11ኛ ለነርሶች ካደረጉት ንግግር የተወሰደ

ከባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትራቸው የተላከው ቴሌግራም እንደደረሳቸው፤ ወዲያውኑ ለቅዱስነታቸው የሚከተለውን መልዕክት ላኩ።

## ለብፁዕ ወቅዱስ ፒዮስ 11ኛ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘመንበረ ጴጥሮስ፤

ቫቲካን ሲቲ

በእኛና በጣልያን መካከል በአሁኑ ሰዓት የተፈጠረው ችግር በሰላማዊ መንገድ ማለቅ ያለበት መሆኑን በመግለጽ፤ ቅዱስነትዎ የሰጡትን ማሳሰቢያና የገለጹትን አስተያየት ተመልክተን፤ ከፍ ያለ ምስጋናችንን እንልክልዎታለን። በዚህም አጋጣሚ ኢትዮጵያ እስካሁን ድረስ ያለማቋረጥ ለሰላም ያደረገችውን ብርቱ ጥረት፤ እስከ መጨረሻው የምትቀጥል መሆኗን ቅዱስነትዎ እንዲያውቁት ልናረጋግጥልዎ እንወዳለን።

*ፊርማ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ንጉሠ ነገሥት*

ይህ ጃንሆይ ለሮማው ርዕሰ ጳጳስ ከአዲስ አበባ የላኩት ቴሌግራም ቫቲካን ሲቲ ከመድረሱ በፊት፤ በፋሽስቶች ኢንተሊጀንስ ሰርቪስ ተጠልፎ ለቤኒቶ ሙሶሊኒ ስለደረሰው፤ ዱቼ እጅግ ተናደደ። ፒዮስ 11ኛ በመንግሥታችን ጉዳይ ውስጥ ገብተው ለጠላታችን ወገን ረዳት ሆነው መገኘታቸው የሚያሳዝን ነው ካለ በኋላ፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩን ጠርቶ በአስቸኳይ ለቫቲካን አስተዳደር አንድ የተቃውሞ መግለጫ (ኖት ቬርቫል) እንዲላክ ትዕዛዝ ሰጠ። ይህም ኖት ቬርቫል፤ ፒዮስ 11ኛ ለዓለም ነርሶች ያደረጉት ንግግር፤ የፋሽስቱን መንግሥት ምን ያህል እንደአሳዘነውና ለወደፊቱም ይህን የመሰለው ሁኔታ እንዳይደገም የሚያስጠነቅቅ እንዲሆን የተዘጋጀ ነበር። ቃሉም የሚከተለው ነው። " ... ፒዮስ 11ኛ ከሦስት ቀናት በፊት የዓለምን ነርሶች ሲቀበሉ ያደረጉት ንግግር፤ በአሁኑ ጊዜ የምንከተለውን ፖለቲካ እጅግ አድርጐ የሚያወግዝ ነው በማለት፤ የጣልያንና የፋሽስት ተቃሚዎች በሆኑት የዓለም ጋዜጦች በሰፊው ተተችቶበታል። በተለይም በእንግሊዙ ማንቸስተር ጋርዲያን (Manchester Guardian) በጀርመኑ የሙኒክ ዘይቱንግ (Munchner Zeitung) በጣልያንና ፋሽስታዊ በሆነው መንግሥታችን ላይ ያላቸውን የጠበቀ ጥላቻቸውንና ተቃውሞአቸውን ለመግለጽ ምክንያት ሆኗቸዋል። ፒዮስ 11ኛ ለነርሶቹ ባደረጉት ንግግር፤ የፋሽስት ጣልያንን እቋምና ዕምነት በመጻረር፤ ወራዶች የሆኑትን የነዳጅ ዘይት ኩባንያ ቡድኖች ጥቅም ለመጠበቅ ለሚጥሩት የፕሬስ ድርጅቶች የሚረዳ ሆኖ መገኘቱ ጥርጥር የለውም። አሁን ለዚህ ላለፈው ጉዳት ምንም ዓይነት መድኃኒት ባይገኝለትም፤ የጣልያን ፋሽስታዊ መንግሥት የቫቲካንን አስተዳደር አጥብቆ የሚጠይቀው ወደፊት በቅርቡ ስለሚከናወነው ጉዳይ ነው። ይኸውም፤ በሚቀጥሉት ጥቂት ቀናቶች ውስጥ ካቶሊኮች የሆኑት የጣልያን የቀድሞዎቹ ጀግኖች ወታደሮች ቅዱስነታቸው ዘንድ ቀርበው ቡራኬ እንደሚቀበሉ ይጠበቃል። በዚህ ዕለት ፒዮስ 11ኛ የሚያደርጉት ንግግር፤ እንደአለፈው እንደ ነርሶቹ ጊዜ፤ የጣልያንን ፋሽስታዊ መንግሥት ጠላቶች የሆኑትን ሁሉ የሚረዳና እንዲሁም በቫቲካንና በእኛ መካከል በ1931 ዓ.ም የተመሠረተውን የወዳጅነት ግንኙነቶችና ስምምነቶች የሚያበላሽ እንደማይሆን ተስፋ ያደርጋል ... " ይህ በሙሶሊኒ ትዕዛዝ ተዘጋጅቶ የተላከው ኖት ቬርቫል ከቫቲካን አስተዳደር ጽሕፈት ቤት ሲደርስ፤ ከስቴት

ሴክረተሪው (ማለት ጠቅላይ ሚኒስትሩ) ጀምሮ ያሉት ባለሥልጣኖች በሙሉ ከፍ ያለ ድንጋጤና ጭንቀት ላይ ወደቁ። እንግዲህ ! ምን ማድረግ ይሻለናል እያሉ ታላላቆቹ ካርዲናሎች በሚወያዩበት ጊዜ፣ የቫቲካን ልሳን የሆነው፣ "ኦብሴርቫቶሬ ሮማኖ" (Observatore Romano) የተባለው ጋዜጣ፣ ፖፑ ለነርሶቹ ባደረጉት ንግግር አቋማቸው ምን እንደነበረ በተሻለ መንገድ ለማብራራትና የሙሶሊኒን ቁጣ ለማብረድ አንድ ዓይነት ሙከራ አደረገ።

በ "ኦብሴርቫቶሬ ሮማኖ" ላይ ዋናው አዘጋጅ ባቀረበው ጽሑፍ፣ ፒዮስ ፲፩ኛ በቃላቸው ባደረጉት ንግግር፣ የማንም ደጋፊ ወይም የማንም ተቃዋሚ ለመሆን አለማሰባቸውን ካስረዳ በኋላ፣ ስለገለጹት አስተያየት ፍሬ ነገሩን ጨምቆ ያቀረበው በሚቀጥለው አኳኋን ነበር። " ... በአንዳንድ አገሮች ከቦታ ጥበት የተነሣ በሕዝቦች ላይ የሚደርሰውን የኑሮ ችግር ለማሻሻል ሰፋ ያለ ግዛት ማግኘት አስፈላጊ ይሆናል ቢባልም፣ ለግዛት ማስፋፊያ ተብሎ የሚወሰደው የጦርነት እርምጃ መብት ሆኖ ሊቆጠር አይችልም። በሌላ በኩል ደግሞ በእርግጥ፣ የራስን ግዛት ከውጭ ወራሪ ለመከላከል የሚደረግ ጦርነት መብት መሆኑ አይካድም። ይሁን እንጂ፣ የመከላከሉም ጉዳይ ቢሆን፣ በሰላማዊ መንገድ እንዲፈታ ጥረት ሳይደረግበት የጦርነትን እርምጃ መውሰድ ከባድ ስሕተት ሊያስከትል እንደሚችል መታሰብ አለበት ... " በማለት ፒዮስ 11ኛ ምክራቸውን ሰጥተዋል ሲል ኦብሴርቫቶሬ ሮማኖ የሰጠው ማብራሪያ፣ የዱቼን መንግሥት የበለጠ የሚያበሳጭ እንጂ አስተያየቱን የሚያለሰልስ፣ ወይም ወደ ይቅርታ የሚመልስ መሆን አልቻለም። በተጨማሪም፣ በገቢኔቭ ያሉት የመንግሥታት ማህበር እንደራሴዎችና አብዛኛዎቹ የአውሮፓ ጋዜጦች፣ ፒዮስ ፲፩ኛ የሰጡትን አስተያየት በመደገፍ ስለ አሟሟቁት ዱቼን እጅግ አድርጎ አስቆጥቶታል።

ቅዱስነታቸው ግልጽና እውነተኛ በሆነ መንገድ ያደረጉት ንግግር፣ የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ጦርነት ለመክፈት የሚያደርገው ዝግጅት፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን የተመሠረተበትን ዓላማ የሚጥስ ከመሆኑም በላይ፣ መዘዙ ለዓለም ሰላም ጠንቅ መሆኑን ስለሚያመለክት፣ በሰላማዊ መንገድ እንዲያልቅ አጥብቆ የሚያሳስብ ነው። በዚህም መሠረት ከቅዱስነታቸው የተሰጠውን ማሳሰቢያ በአክብሮት የሚቀበሉትና የሚደግፉት በገቢኔቭ ያሉት የመንግሥታት ማህበር እንደራሴዎች ብቻ ሳይሆኑ፣ የክርስትናን ዕምነት የሚከተሉት አገሮችና እንዲሁም በክርስቲያንነቱ ታውቆ የሚኖረው የጣልያንን ሕዝብ ጭምር ነው እየተባለ በሰፊው ተነገረ። ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው ልዩ ልዩዎቹ የአውሮፓ ጋዜጦችም በየፊናቸው አስተያየታቸውን ከመስጠት አልተቆጠቡም።

- ላ ክርዋ (La Croix) የተባለው የፈረንሣይ ካቶሊክ ጋዜጣ፣ ነሐሴ 31 ቀን 1935 ዓ.ም በጻፈው ርዕሰ አንቀጽ፣ " ... ፒዮስ 11ኛ በወሰዱት ግልጽ የሆነ አቋም፣ ግዛት ለማስፋፋት የሚደረገውን ጦርነት ሁሉ አጥብቀው ካወገዙ በኋላ፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረው ጠብ በሰላማዊ መንገድ መፍትሔ እንዲያገኝ የሰጡትን ማሳሰቢያ መከተል ያስፈልጋል ሲል ሐተታውን ደምድሟል።

- ታይምስ "Times" የተባለው የእንግሊዝ ጋዜጣ በበኩሉ አስተያየቱን ሲሰጥ፣ በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል ስላለው ጉዳይ ቅዱስነታቸው የሰጡት መግለጫ፣ የሙሶሊኒ እሥረኛ አለመሆናቸውንና ነፃነታቸውን መጠበቃቸውን ደህና አድርጎ የሚያስገነዝብ ነው ብሏል።



የሚላኖው ሊቀ ጳጳስ ካርዲናል ኢልዴፎንስ ሹስተር፤ የፋሽስት መንግሥት ደጋፊነታቸውን በግልጽ አስረድተዋል። “ ... የጣልያን መንግሥት በኢትዮጵያ ምድር የባርነትን አገዛዝ ሰንሰለት በመጣስ ፤ የካቶሊክን ተልዕኮ የተቀበለ ነው ... ” ሲሉ የሚላኖ ሊቀ ጳጳስ በተናገሩት፤ ፒዮስ 11ኛ እጅግ ማዘናቸውን ገልጠዋል። የሚላኖው ሊቀ ጳጳስ የተናገሩትም በግላቸው እንጂ በመንበረ ጴጥሮስ ስም አለመሆኑን የቫቲካን መሪዎች በይፋ አስታውቀዋል።

ፎቶግራፉ የሚያሳየው ካርዲናል ሹስተር፤ የፋሽስት ደጋፊነታቸውን ሲያስረዱ ነው፤

- ዘይቱንግ የተባለው የጀርመን ጋዜጣና የእንግሊዙ ማንቸስተር ጋርዲያን (Manchester Gardian) የሙሶሊኒ መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ያቀደውን ጦርነት በማውገዝ፣ ፒዮስ 11ኛ ያደረጉትን ንግግርና ያሳዩትን የአቋም ጥንካሬ አድንቀው እንደጻፉት ሁሉ፣ በፈረንሣይና በቤልጊክ የሚታተሙትም ጋዜጦች፣ አስተያየታቸውን ተመሳሳይ በሆነ መልክ ሰጥተዋል፡፡ " ሌሎች ደግሞ እንደ "አዲሲቷ መሬት" (Terre Nouvelle) የመሳሰሉት ክርስቲያናዊ ሬቮሊሽነሪ ነን የሚሉት ጋዜጦች፣ ፒዮስ 11ኛ ለዓለም ነርሶች ያደረጉት ንግግር በኢትዮጵያ ላይ ሙሶሊኒ የሚያዘጋጀውን ጦር በሚገባ ያወገዘና ተቃውሞውን በጥንካሬ የገለጸ አይደለም በማለት ተችተዋል፡፡ እነዚህ የግራ ክንፍ የሆኑት ጋዜጦች አስተያየታቸውን ሲያብራሩ፣ የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ መሪ፣ ለመላው ዓለም ሕዝብ ማስረዳት ያለባቸው፣ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመውረርና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ የሚያዘጋጀው ጦር፣ ለዓለም ሰላም ጠንቅና ሕገ ወጥ መሆኑን ነው እንጂ፣ ጉዳዩ በሰላማዊ መንገድ መፍትሔ እንዲያገኝ ያስፈልጋል ማለት ብቻ፣ በቂ አይደለም በማለት ቅሬታቸውን ገልጸዋል፡፡ "

ከግራ ክንፍ ወገኖች ለተጻፈው ይህን ለመሳሰለው አስተያየት መልሱን ለመስጠት ጥረት ያደረጉት ጋዜጦች ጥቂቶች አይደሉም፡፡ የአብዛኛዎቹም አስተያየት የሚከተለው ነበር፡፡ " ... **የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ መሪ፣ ነሐሴ 27 ቀን ለነርሶቹ ካደረጉት ንግግር የበለጠ መናገር አይችሉም፡፡ ለግዛት ማስፋፊያ የሚደረግ ጦርነት፣ "ፍትሐዊ አይደለም" ብሎ ከማውገዝ ሌላ ምን መጨመር ይችላሉ ?** ... ይህንን እንኳ መናገራቸው መንፈስ ቀራጥ በመሆናቸው ነው እንጂ፣ ከዲክታተሩ ፋሽስት ጋር የሚገጥሙት ጦርነት ለቫቲካን እጅግ አደገኛ መሆኑን ዘንግተውት አይደለም፡፡ ... ቅዱስነታቸው ነሐሴ 27 ቀን ለነርሶቹ ቡራኬ ተዘጋጅቶ ከቀረበላቸው ዲስኩር ውጭ፣ ስለኢትዮጵያ ጉዳይ በቃላቸው ጨምረው የተናገሩትን ቀደም ብለው ለረዳቶቻቸው አማክረዋቸው ቢሆን ኖሮ፣ ፋሽስቱ መሪ በቫቲካን ላይ የሚያደርሰውን አደጋ በማየት፣ ረዳቶቻቸው ካርዲናሎቹ በሙሉ በአንድ ቃል፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ ጉዳይ እንዳይናገሩ ይማጸኗቸው ነበር፡፡ ቅዱስነታቸውም የረዳቶቻቸውን አስተያየት በቅድሚያ ስለሚያውቁ፣ ማንንም ሳያማክሩ በነሐሴ 27 **ቀን 1935 ዓ.ም የሚያስቡትንና በተለይም ራሳቸው ያዘጋጁትን ሐሳብ ወረወሩ፡፡** ... "

እርግጥ ነው! ፒዮስ 11ኛ ለነርሶቹ ያደረጉት ንግግር ከዲክታተሩ መንግሥት ጋር ጠብ ለመጫር ሳይሆን፣ በሃይማኖት መሪነታቸው በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ያለው አለመግባባት በሰላም መንገድ እንዲፈታ ተግባራቸውን ለመፈጸም በማሰብ ነበር፡፡ እንደሚታወቀው፣ ዱቼ ይህን የመሰለውን ሐሳብ አለመቀበል ብቻ ሳይሆን፣ መስማትም አይፈልግም፡፡ **የዱቼ ግቡ የአድዋን ብድር መመለስና ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ አድርጎ መያዝ ነው፡፡** ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ፒዮስ 11ኛ፣ በፋሽስት መንግሥት ጉዳይ ውስጥ ገብተው በቀጥታ ሆነ ወይም ቀጥታ ባልሆነ መንገድ አስተያየት መስጠት አይፈቀድላቸውም በማለት ለጋዜጠኞች በሚያስረዳበት ጊዜ፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ከአንድ አገር መሪ የማይጠበቅና አሳዛኝ የሆነ አንድ መግለጫ ሰጠ፡፡ ይህም ቃል የሚከተለው ነበር፡፡ * " ... **በፋሽስት መንግሥታችን ዘንድ የመንበረ ጴጥሮስ ቤተክርስቲያን ምንም ዓይነት ሉዓላዊነት**

---

* MAX GALLO L'ITALIE DE MUSSOLINI (PAGE 224)

አልተሰጠውም። ከዚህም በላይ ምንም ዓይነት ነፃነት የለውም። መሠረታዊ ታሪኩ እንደሚያስረዳው፣ በእርግጥ፣ የክርስቲያን ሃይማኖት በፓሌስቲን ተወልዶ፣ ሮም ላይ ካቶሊክ ሆኗል። የጣልያንም ሕዝብ የካቶሊክነት ዕምነት የተቀበለው ከዚህ የተነሣ ነው። ሆኖም፣ ጣልያን ከሁሉ በፊት ያላት መታወቂያዋና ክብሯ ፋሽስትነቷ ነው እንጂ፣ ካቶሊክነቷ አይደለም። እኛና ፋሽስታዊው መንግሥታችን ከቀድሞው ዘመን ሲያያዝ የመጣውን የፓፓዎቹን ሥልጣን በሚገባ ቀብርነው እንጂ፣ እንደገና ሕይወት እንዲዘራ ዕድል አልሰጠነውም። ስለዚህም፣ ፋሽስታዊቷ ጣልያን ዛሬም ሆነ ወደፊትም ፋሽስት ነች። በፋሽስትነቷም ለምንጊዜውም ጸንታ የምትኖር ነች። የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ መሪዎችም፣ በ1929 ዓ.ም በፋሽስታዊው መንግሥታችን አመራር በፊቃዳችን የሰጠናቸውንና ያደረግንላቸውን "የላትራን ስምምነቶች" (accords du latran) ጠብቀው በሰላም እንዲኖሩ ጠይቀናቸዋል። ስለዚህም ከእንግዲህ ወዲህ ምርጫው የእነሱ ነው። የግዛት ማስፋፊያ ጦርነት፣ የመከላከያ ጦርነት፣ ፍትሐዊነቱ በዚህና በዚያ ነው እያሉ፣ ከሃይማኖት ተግባራቸው እየወጡ፣ በመንግሥታችን ጉዳይ እየገቡ ፍርድ ሰጭ መሆን የለባቸውም። ይህንንም እንዲያቆሙ በሚገባ ተናግረናል። መደጋገም የለብንም ...
"

ይህ የሙሶሊኒ መግለጫ፣ የቫቲካን መሪዎችን ብቻ ሳይሆን የመላው የካቶሊክ ሃይማኖት ተከታዮችን ሁሉ ከፍ ያለ ድንጋጤ ላይ ጥሏቸዋል። ስለዚህም፣ ከእንግዲህ ወዲህ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ፒዮስ 11ኛ በኢትዮጵያና በጣልያን ጉዳይ የዱቼን ዕቅድና እርምጃ ለመደገፍ ካልሆነ በስተቀር፣ ከዚህ በፊት እንዳደረጉት በዳኝነት መንፈስ ምንም ዓይነት አስተያየት ከመስጠት ታግደው ድምፃቸውን አጥፍተው እንዲቀመጡ የሚያስገድዳቸው ሆነ። በዚህ ዓለም በአንዳንድ አገሮች ላይ በጉልበት ሥልጣናቸውን አስፋፍተው ሕዝቡን እንደ አሰኛቸው የሚመሩት ዲክታተሮች፣ የፈለጉትን ከማድረግ የሚያግዳቸው እንደሌለ፣ ባለፉት ዘመናት የደረሱት ሁኔታዎች ያስረዳሉ። ለምሳሌም ያህል፣ ፈረንሣዊው ናፖሊዮን ቦናፓርት (Napoleon Bonaparte) በ1809 ዓ.ም ከመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ መሪ ከፒዩስ 7ኛ ጋር ሳይግባባ ስለቀረና ፖፑም ሥልጣናቸውን ለመከላከል ስለተቋቋሙት፣ ዲክታተሩ መሪ ወታደሮች ልኮ ከሮም መንበራቸው አስነሥቶ ጀኖዋ ከተባለው አውራጃ አጠገብ በሚገኝ ቦታ በግዞት እንዲኖሩ ፈረደባቸው። ፒዮስ 11ኛም እንደ ፒዮስ 7ኛ ከሙሶሊኒ ጋር መጋተርን ቢመርጡ፣ ምንም እንኳ ከመቶ ዓመታት በፊት ናፖሊዮን እንዳደረገው ዱቼ በፋሽስት ወታደሮቹ አስገድዶ ወደ ግዞት ባይልካቸውም፣ የላትራንን ስምምነት አፍርሶ የቫቲካንን አስተዳደር መብት በመግፈፍ ምንም ዓይነት እንቅስቃሴ እንዳያደርጉ አሥሮ ሊያስቀምጣቸው ይችላል። ስለዚህም የዓለም ካቶሊኮች አባት፣ ከፋሽስቱ ዲክታተር መሪ ጋር ተጣልተው ከባድ ችግር ላይ ከመውደቅ፣ በኢትዮጵያ ጉዳይ ከእንግዲህ ወዲህ ምንም ዓይነት ፍትሕን የተመረኮዘ አስተያየት ከመስጠት ታግደው መኖር የሚሻል ሆኖ ታያቸው።

## ቅዱስ አባታችን ምነው ዝም አሉ?
## እባክዎ ይናገሩ?

እ.ኤ.አ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም የፋሽስት ጦር ከኤርትራና ከሱማሌ ተነሥቶ በሰሜንና በደቡብ በኩል በከፍተኛ ደረጃ በተዘጋጀ ጦር ኢትዮጵያን ሲወጋ፣ በአውሮፓ የሚገኙት ልዩ ልዩ የሃይማኖትና የመንፈሳዊ ድርጅቶች፣ እንዲሁም የሰብአዊ ተግባር ፈጻሚዎች፣ ለመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ቤተክርስቲያን መሪ ለፒዮስ ፲፩ኛ እያከታተሉ የሚልኳቸው ልዩ ልዩ ቴሌግራሞች፣ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ

የሚፈጽመውን የግፍ ሥራ ቅዱስነታቸው እያወገዙ፣ ለመላው ዓለም እንዲያስታውቁ ተማጸኗቸው። ከሃይማኖት አባቶችም መካከል፣ እንግሊዝ አገር ያሉት የካንተርበሪው ሊቀጳጳስ ለቫቲካን በላኩት ልዩ መልዕክት፣ ፒዮስ 11ኛ ፋሽስት በኢትዮጵያ ላይ የጀመረውን ጦርነት እንዲያቆም ለዓለም ሕዝብ በግልጽ መናገር አለባቸው ሲሉ አሳሰቡ። የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ መሪም ወዲያውኑ በሰጡት መልስ፣ " ... በእኛ በኩል ከዚህ በፊት በነሐሴ 27 ቀን ከገለጽነው አስተያየት የምንጨምረው የለም ... " በማለት አስታወቁ።

ይህንን ከፒዮስ 11ኛ ለካንተርበሪው ሊቀ ጳጳስ የተሰጠውን መልስ በማብራራት በቫቲካን ላይ ያለውን ችግር ለማስረዳት አብዛኛዎቹ ካቶሊካዊ ድርጅቶች ብዙ ጥረት አድርገዋል። " ... ቅዱስነታቸው በዛሬው ሰዓት የሚገኙበትን እጅግ አስቸጋሪ ሁኔታ መገንዘብ ያስፈልጋል። ማንም ሰው በቀላሉ እንደሚረዳው፣ የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ቤተክርስቲያን እንደ አንድ አገር መንግሥት ነፃነቷ የተጠበቀና ለመከላከያዋም የጦር ድርጅት ያላት አይደለችም። ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሱም፣ ለፀጥታቸው መጠበቂያ ያላቸው ቁጥራቸው ከአንድ መቶ የማይበልጡ የስዊስ ዘበኞች ብቻ ናቸው። በ1929 ዓ.ም በፋሽስቱ መንግሥትና በቫቲካን መካከል የተደረገው ስምምነትና የተፈረመው ውል ምንና ምን መሆኑን በጥልቀት ለሚመለከተው፣ የካንተርበሪው ሊቀ ጳጳስ እንደአሳሰቧቸው የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ መሪ ሙሶሊኒን በአደባባይ ወጥተው ማውገዝ የማይቻላቸው መሆኑን መገንዘብ አያዳግትም። የካንተርበሪው ሊቀ ጳጳስ እንግሊዝ አገር በሚገኘው መንበራቸው ላይ ሆነው፣ የፋሽስቱ መንግሥት የሚያደርገውን ሁሉ ማውገዝ እንደሚችሉ ለማንም ግልጽ ነው። የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ መሪ ግን ሮማ ሆነው የፋሽስቱ መንግሥት ወደ ሰላም ጉዳና እንዲያመራ ከመምከር በስተቀር፣ አድራጐቱን ተቃውመው ለመውቀስም ሆነ ለመኰነን ይችላሉ ብሎ ማሰብ ሚዛን ያለው አስተያየት አይደለም። ለምሳሌም ያህል በነሐሴ 27 ቀን 1935 ዓ.ም ቅዱስነታቸው በሰጡት መግለጫ፣ ለግዛት ማስፋፊያ የሚደረግ ጦርነት ሁሉ ፍትሐዊነት የሌለው መሆኑን በማስረዳታቸው ብቻ፣ ከፋሽስቱ መንግሥት የደረሳቸው ማስጠንቀቂያ እስከምን ድረስ እንደሆነ መመዘን ይገባል ... "

ይህንን ካቶሊኮቹ የሰጡትን ማብራሪያ ብዙዎቹ ቢቀበሉትም፣ አንዳንዶቹ አንስማማም ከማለት አልተቆጠቡም። በተለይ ሙሴ ኤሪክ ሊንዱርም (Eric Lindum) የተባለ ስዊድናዊ ጋዜጠኛ፣ ለቫቲካን ጽፎ በላከው ደብዳቤ፣ በኢትዮጵያ ጉዳይ ፒዮስ 11ኛን እጅግ አድርጐ ወቅሷል። ይኸውም፣

1ኛ/ ቅዱስነትዎ ከእግዚአብሔር የተሰጠዎትን ተግባር ትተው፣ ሙሶሊኒን እንደ ጣኦት አድርገው በመቀበል ሰግደውለታል።

2ኛ/ ከእግዚአብሔር የታዘዙትን የፍርድ ሥራ ዘንግተው፣ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመውጋት የወሰደውን እርምጃ ሳይቃወሙት በመቅረትዎ ፈጣሪዎን ከድተዋል።

3ኛ/ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን በግፍ በመውረሩ፣ የዓለም መንግሥታት የፈረደበትን የኢኮኖሚ ጭቆና ለማስፈጸም፣ የበኩልዎን እርዳታ ሳያበረክቱ በመቅረትዎ እጅግ የሚያሳዝን ተግባር ሠርተዋል። ....

በማለት፣ በእነዚህ ከዚህ በላይ በተጠቀሱት ሦስት ዋና ዋና ሐሳቦች ላይ ስዊድናዊው ጋዜጠኛ ቅሬታውን እየተነተነ፣ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሱን እጅግ በከረሩ

ቃላቶች ከወቀሰ በኋላ አስተያየቱን ሲደመድም፤ " ... ቅዱስነትም የዓለምን ሰላም የሚያደፈርሰውን ወንበዴውን ሙሶሊኒን ቢያወግዙት ኖሮ፤ እርስም ለሚመሩት ቤተክርስቲያን ምን ያህል ጥቅም በሰጠ ነበር። ይህንን በመፈጸምም ዲክታተሩ ቢያስርም፤ ክርስቲያኖችን ለሰማዕትነት እንዳበቋቸው ይቆጠርልም ነበር። የመላው ዓለም ሕዝብም ከእርስም ጋር ይሆን ነበር። እርስም ግን እስከዚህ ድረስ ቆርጠው መሥዋዕትነትን መቀበል ካለመፈለግዎም በላይ፤ ለዚች ግፍን ለምትቀበል ኢትዮጵያ አንዳች ነገር ሳያደርጉላት በመቅረትም እጅግ የሚያሳዝን ነው ... " ብሏል።

ኤሪክ ሉንዱርም፤ ይህንን ወቀሳ ለሮማው ፓፓ ልኮ በብዙዎች ጋዜጦች እንዲሁም በኢትዮጵያ በብርሃንና ሰላም ላይ ታትሞ ሲወጣ፤ በሐረር የሚገኙት የካቶሊካዊት ቤተክርስቲያን ሚሲዮን ኃላፊ የሆኑትና ቀድሞም የተፈሪ መኮንን (ኋላ ቀ.ኃ.ሥ) ፈረንሣዊኛ መምህር የነበሩት አቡነ እንድርያስ ዣሮሶ (Andre Jarosseau) የሚከተለውን መልስ ሰጥተዋል። አቡነ ዣሮሶ ለስዊድኑ ጋዜጠኛ የሰጡት መልስ፤ በኢትዮጵያና በቫቲካን ጉዳይ እሳቸው ራሳቸው በትክክል አውቃለሁ የሚሉትንና ምስክርነታቸውን የሚገልጽ ስለሆነ፤ በብርሃንና ሰላም ጋዜጣችን ላይ ታትሞ እንዲወጣላቸው ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልካም ፈቃዳቸውን ሰጥተውላቸዋል።

**የአቡነ እንድርያስ ዣሮሶ መልስ**

## ለክቡር አቶ ማሕተመ ወርቅ እሸቴ የብርሃንና ሰላም ጋዜጣ ዲሬክተር

የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ቤተክርስቲያን አባት መሪ የሆኑትን የፒዮስ ፲፩ኛን ክብር በማጉደፍ፤ ሙሴ ኤሪክ ሉንዱርም የጻፈውንና በብርሃንና ሰላም ጋዜጣ የታተመውን በሚገባ አንብቤለሁ። ሙሴ ኤሪክ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ያለውን ኃዘኔታና መልካም አስተያየት አደንቃለሁ። ነገር ግን፤ ቅዱስ ፓፓው በኢትዮጵያና በጣልያን ጉዳይ ምንም አልሠሩም ብሎ የሚወቅሳቸውንና፤ ለፋሽስቱ መሪ ለሲኞር ሙሶሊኒ ይሰግዳሉ ብሎ የሚዘልፋቸውን ስመለከት፤ ሙሴ ኤሪክ ብዙ ያልተረዳቸው ነገሮች ስላሉ መልሱን በአግባቡ መስጠት ግዴታዬ ሆኗል። ስለዚህም፤ የማቀርበው አስተያየት ታትሞ እንዲወጣልኝ በማክበር እጠይቃለሁ።

" ... ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመውጋት ከሚደራጅበት ጊዜ ጀምሮ፤ ቅዱስ አባታችን ፒዮስ 11ኛ፤ ሰላም እንዲፈጠር ከመጸለይና ከመጨነቅ አቋርጠው አያውቁም። ይህ የጦርነት መቅሠፍት በኢትዮጵያ ላይ እንዳይወድቅ የሚቻለኝን ሁሉ ለማድረግ ቁርጥ ሐሳብ ያለኝ መሆኔን ለንጉሠ ነገሥቱ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አስረዳልኝ ሲሉ አዘውኝ፤ ትዕዛዛቸውን ፈጽሚያለሁ። በተጨማሪም ለሰላም የምናደርገው ጥረት ሁሉ መልካም ፍሬ እንዲሰጥ፤ በኢትዮጵያና በቫቲካን መካከል የዲፕሎማቲክ ግንኙነት እንዲከፈት የቅዱስነታቸው ጽኑ ፍላጐት ስለነበረ፤ ለጃንሆይ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አቅርቤ፤ ጉዳዩ ወደፊት የሚታሰብበት መሆኑ ተገልጾልኛል።

ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱን ከመከፈቱ በፊት፤ ቅዱስ ፓፓው ከአንድም ሁለት ጊዜ በሰጡት መግለጫ፤ ግዛትን ለማስፋፋት የሚደረግ ጦርነት ሁሉ ፍትሐዊነት የሌለውና መብትም አለመሆኑን ደህና አድርገው በማስረዳት

አውግዘዋል። ይህንንም የመላው አውሮፓ ጋዜጦች በጻፉት ውስጥ የቅዱስ ፓፓውን ብርታትና ጥንካሬ አድንቀዋል።

ሙሴ ኤሪክ ንቀፋውን በመቀጠል፤ በገኔቭ ያለው የመንግሥታት ማህበር በሙሶሊኒ መንግሥት ላይ የፈረደውን የኢኮኖሚ ጭቆና ቅዱስነታቸው ተስማምተው ሳይፈጽሙ ቀርተዋል ብሎ ይወቅሳቸዋል። ሙሴ ኤሪክ እንደዚህ ሲናገር፤ ጉዳዩን በምን መልክ እንደ ተረዳው ሊገባኝ አልቻለም። ቫቲካን የአንድ አገር መንግሥት አይደለም። የመንግሥታት ማኅበርም አባል አይደለም። በሙሶሊኒ አስተዳደር ላይ የተፈረደውን የኤኮኖሚ ጭቆና የሚተባበርበትም ሆነ የሚቃወምበት መንገድ የለውም። ስለዚህ፤ ሙሴ ኤሪክ የሚነቅፈውንና የሚደግፈውን በትክክል ለይቶ ማወቅ የሚገባው ይመስለኛል። በእኔ በኩል በማውቀውና ባለብኝም ኃላፊነት፤ ቅዱስ ፓፓው ለኢትዮጵያ ያላቸውን መልካም አመለካከትና ወዳጅነት አንድም ጊዜ አለማቋረጣቸውንና አለመለወጣቸውን ለኢትዮጵያ ሕዝብ ማረጋገጥ እወዳለሁ። ቅዱስነታቸው ለባለታሪኩ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ያላቸውን አክብሮትና ፍቅር ያረጋገጡበትን አንድ ቁም ነገር መርሳት አይገባም። በአሁኑ ሰዓት በቫቲካን ቅጥር ግቢ ውስጥ የሚገኘውን የኢትዮጵያ ኮሌጅ በ1929 ዓ.ም ሕንፃውን የሠሩና ያቋቋሙ ፒዮስ 11ኛ ናቸው። ቀጥሎም፤ ከሙሶሊኒ መንግሥት ጋር በላትራን በተደረገው ስምምነት መሠረት፤ በቫቲካን ግቢ ውስጥ የነበሩት የልዩ ልዩ አገር ኮሌጆች ሁሉ እንዲወጡና ወደ ሮማ ከተማ እንዲዛወሩ ሲደረግ፤ "በነጭ ባሕር ውስጥ አንድ ጥቁር ነጥብ ውበት የሚሰጥ ጥሩ ምልክት ስለሆነ፤ የኢትዮጵያ ኮሌጅ ከቫቲካን ግቢ ውስጥ መውጣት የለበትም" ብለው በመወሰን፤ እስከዛሬ ድረስ እንዲቆይ ያስደረጉት ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ፒዮስ 11ኛ ናቸው። በዚህ ኮሌጅ ውስጥ የሚማሩትን ወጣቶች እንዲሁም ከአገራቸው ብዙ ሺህ ኪሎ ሜትር ተጉዘው የቅዱስ ጴጥሮስን መካነ መቃብርና ቤተክርስቲያን ለመጎብኘት የሚመጡትን ኢትዮጵያውያን ካህናትና ምዕመናንን ቅዱስነታቸው እየተቀበሉ በማነጋገር፤ መድኃኒታችን መድኃኔዓለምና ቅድስት እናቱ፤ ኢትዮጵያንና መልካሙን ንጉሠ ነገሥቷን ምንም ሳይነካቸው እንዲጠብቋቸው ከመጸለይና ቡራኬ ከመስጠት አላቋረጡም።

እንግዲህ! ሙሴ ኤሪክ ቅዱስ ፓፓ ቁማር እንዳልሆኑ፤ ለቁማርም እንዳልሰገዱ፤ ፍጹም የሕዝብ አገልጋይ መሆናቸውን እንዲገነዘብ እንመኛለን።

ተጻፈ በሐረር እንደ ኢት. አቆ ታህሣሥ 22 ቀን
1928 ዓ.ም አባ እንድሪያስ ዣሮስ

የካቶሊካዊት ቤተክርስቲያን ሐረር ላይ የሚገኘው ሚሲዮን መሪ የሆኑት አቡነ እንድርያስ ዣሮሶ እንደተናገሩት፤ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ፒዮስ 11ኛ ለኢትዮጵያ የሚያስቡና የሚጨነቁ እንደነበሩ የሚያረጋግጡ ብዙ መረጃዎች አሉ። በተለይም፤ ዲክታተሩ ፋሽስት ቤኒቶ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ ድንበር ጥሶ የከፈተውን ጦርነት፤ ቅዱስ ፓፓው ደግፈዋል የተባለውና ከዚህም በላይ የተላከውን የጦር ኃይል ባርከው አሰናብተዋል ተብሎ የተነገረው ሁሉ፤ መሠረት የሌለውና ማስረጃ ያልተገኘለት መሆኑን ባደረግነው ምርምር ለማወቅ ችለናል። እርግጥ ነው! የኢትዮጵያ በጣልያን ይዞታ መተዳደር በአገሪቱ ላይ ለካቶሊክ ሃይማኖት ማስፋፊያና ሕዝቡ ዘመናዊ ሥልጣኔ አግኝቶ ከገባር ጭቆና እንዲላቀቅ የሚረዳ ነው በማለት፤ የፋሽስቱን መንግሥት ፕሮፓጋንዳ እየተከተሉ ምዕመናኖቻቸውን የሰበኩ አንዳንድ ካርዲናሎችና የቤተክርስቲያን ኃላፊዎች መኖራቸው ታውቋል። እነዚህም፤ የሚላኖና የኡዲኔ፤ የሚሲናና የሶሬንቶ፤ የብሪንዲሲና የፓርማ፤ የብሬሻና የፓዶቫ

ሲሆኑ፤ በተለይ በደረጃም ሆነ በኤክስፔሪያንስ ከሁሉም ከፍ ያሉት የሚላኖው ሊቀጳጳስ ካርዲናል ሹስተር (Schuster) ያደረጉትን ንግግር የአውሮፓ ጋዜጦች በብዛት ጠቅሰውታል። " ... የጣልያን መንግሥት በአሁኑ ጊዜ በኢትዮጵያ ምድር ድል አድራጊውን የክርስቶስን መስቀል ይዞ የባርነትን የአገዛዝ ሰንሰለት በመጣስ፤ ለስብከተ ወንጌል መንገድ የከፈተና የካቶሊክን ተልዕኮ የተቀበለ ነው ... " ሲሉ ካርዲናል ኢልዴፎንሶ ሹስተር (Ildefonso Schuster) በአደረጉት ስብከት፤ ቅዱስ ፒዮስ 11ኛ እጅግ አድርገው አዝነዋል። ይህንንም ከሚላኖ ካርዲናል የተነገረውን ቃል ፓፓው ጨርሶ የማይስማሙበትና ተገቢም ያልነበረ ነው በማለት ምን ያህል ቅር እንደተሰኙ፤ በቫቲካን ለተመደቡት የእንግሊዝ፣ የፈረንሣይና የጀርመን የዲፕሎማቲክ ሚሲዮን መሪዎች መግለጻቸውን፤ አምባሳደሮቹ ለየመንግሥታቸው አስታውቀዋል።

ከዚህ በቀር ደግሞ፤ በየከተማው ዋና ዋና አደባባዮች ላይ የፋሽስት መንግሥት እያዘዘ ለጦርነቱ ማፋጠኛና ለድሉ መጕናጸፊያ እያንዳንዱ ሕዝብ ገንዘቡን ብቻ ሳይሆን ጌጣጌጡን ሳይቀር እርዳታ እንዲሰጥ በጠየቀው መሠረት፤ ብዙዎች ካርዲናሎችና ጳጳሳት የጣልያናዊ ዜግነታችንን ግዳጅ መፈጸም አለብን ብለው ከወርቅ የተሠሩትን የአንገት መስቀሎቻቸውን ከነሐብሎቻቸው፤ እንዲሁም የጣት ቀለበቶቻቸውን እያወለቁ፤ በየቀበሌው ለተመደቡት ፋሽስቶች ሲያስረክቡ ታይተዋል። በዚያን ጊዜ በፓሪስ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር የነበሩት ብላቴን ጌታ ወልደማርያም፤ ቫቲካንን እንደ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆነው ለሚያስተዳድሩት ለካርዲናል ፓቼሊ (Pacelli) በአፊሲል ደብዳቤ ባቀረቡት ጥያቄ፤ " ... አንዳንዶቹ ካርዲናሎችና ጳጳሳት በየቤተክርስቲያናቸው በሚያደርጉት ስብከት፤ የፋሽስት ጦር ከኢትዮጵያ ጋር የሚዋጋው ለበጐ ሥራ ነው እያሉ ከመናገራቸው በላይ፤ ለጦርነቱ ድል ማድረጊያ ከወርቅ የተሠሩ ጌጦቻቸውን ሲያበረክቱ ይታያሉ። በዚህ ጉዳይ የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ አቋም ምን እንደሆነ እንዲገለጥልኝ፤ ከንጉሠ ነገሥቴ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ታዝዣለሁ ... " ሲሉ ጠየቁ። ካርዲናል ፓቼሊ (ኋላ ፒዮስ 12ኛ) ለኢትዮጵያዊው ሚኒስትር በሰጡት መልስ፤ " ... አንዳንድ ካርዲናሎች የሚያደርጉት ንግግርና ለጦርነቱ የሚሰጡት እርዳታ፤ የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስን ቤተክርስቲያንና ቅዱስ መሪዋን ፒዮስ 11ኛን የማይመለከት የእያንዳንዳቸው የግል እርምጃ መሆኑን አስታውቃለሁ ... " ብለዋል።

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ በልዩ ልዩ መነሻ በዝርዝር እንደተገለጸው፤ የመላው ዓለም ካቶሊኮች አባት ቅዱስ ፒዮስ 11ኛ፤ ዱቼ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን በቅኝ ግዛት ለመያዝ የሚያደርገውን ጦርነት መደገፋቸውንና ተዋጊዎቹን ወታደሮቹን እንዲሁም መሣሪያዎቻቸውን መባረካቸውን የሚያመለክት አንዳች መረጃ አለመገኘቱ በድጋሚ መታወቅ አለበት። በዚህ ጉዳይ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ያላቸው አስተያየት ምን እንደሆነ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ በሮም አምባሳደራቸው በነበረበት ጊዜ ላቀረበላቸው ጥያቄ፤ ጃንሆይ የሰጡትን መልስ ከዚህ ቀጥሎ ለአንባቢዎቹ ያቀርባል።

# የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አስተያየት

እ.ኤ.አ ታህሣሥ 21 ቀን 1973 ዓ.ም የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና የሱዳን ፕሬዚዳንት ገኔራል ኤል ኑሜሪ፣ በአፍሪካ መንግሥታት መሪዎች ስም ሆነው ስለ ኢየሩሳሌም የወደፊት ዕድል ጉዳይ ከመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ቤተክርስቲያን መሪ ከቅዱስ ጳውሎስ 6ኛ ጋር ለመነጋገር ሮም መጥተው ነበር። የአፍሪካ አንድነት ድርጅት የመሪዎች ጉባኤ ተነጋግሮ በተስማማበት መሠረት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና የሱዳኑ ፕሬዚዳንት ከሮማው ፓፓ ጋር የተነጋገሩት፣ ኢየሩሳሌም የኢንተርናሽናል አቀዋም እንዲኖራትና ሦስቱ የተለያዩ ዕምነት ያላቸው ወገኖች ማለት ክርስቲያኖች፣ እስላሞችና አይሁዶች ወደ ተቀደሰው ሥፍራ በነፃነት ለመግባት እንዲችሉ ለሚደረገው ጥረት የቅዱስ ጳውሎስ ስድስተኛን ትብብርና እርዳታ ለማግኘት ነበር።

ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ቫቲካን የመጡበትን ጉዳይ ከፈጸሙ በኋላ፣ ለሁለት ቀናት ያህል በሮማ የግል ጉብኝት በማድረግ ለመቆየት መልካም ፈቃዳቸው ሆነ። በዚህ ጊዜ ውስጥ የጣልያን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሲኞር አልዶ ሞሮ ታህሣሥ 22 ቀን 1973 ዓ.ም እሁድ ባደረጉላቸው የምሳ ግብዣ ላይ ለመገኘት፣ ቪላ ማዳማ ወደተባለው ሥፍራ ከመሄዳቸው በፊት፣ ንጉሠ ነገሥቱ በማረፊያ ሆቴላቸው ሆነው እኔን አምባሳደራቸውን አስጠርተው በሚከተሉት ጉዳዮች ላይ አነጋገሩኝ።

ጃንሆይ፣ በእኛና በቫቲካን መካከል ስላለው የወዳጅነት ግንኙነት በአንተ በኩል እስከምን ድረስ ተከታትለሃል?

ደራሲው፣ ጃንሆይ እንደሚያውቁት ለእኔ ኃላፊነት የተሰጠኝ ለጣልያን ጉዳይ ነው። ለቫቲካን የተመደቡት ክቡር አምባሳደር አባተ አግዴ ናቸው። ሆኖም በሁለታችን መካከል ደህና መግባባትና መቀራረብ ስለአለ፣ በየጊዜው እየተገናኘን ሐሳብ ለሐሳብ በመለዋወጥ እንሠራለን። ለምሳሌም ያህል ግርማዊነትዎ በትናንትናው ዕለት ያከናወነውን የቫቲካን ጉብኝት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ክቡር ዶክተር ምናሴ ኃይሌ በሰጡን መምሪያ መሠረት ያዘጋጀነው ሁለታችንም ተረዳድተን ነው።

ጃንሆይ፣ የእኛን የትናንትናውን ጉብኝት እንደዚህ ተባብራችሁና ተረዳድታችሁ ያዘጋጃችሁት ከሆነ፣ በመጨረሻው ምን የጐደለ ነገር ታያችሁ?

ደራሲው፣ በዝግጅቱ ላይ ችግር አጋጥሞን የነበረው ስለ አቀባበሉ በፕሮቶኮል ረገድ የታሰበው ሥነ ሥርዓት ነበር። የቫቲካን ታላላቆቹ ኃላፊዎች በተለይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ጠርተው እንዳስረዱን፣ ቅዱስ ፓፓው ግርማዊ ንጉሠ ነገሥትን የሚቀበሏቸው በጽሕፈት ቤታቸው መግቢያ በር ላይ እንጂ፣ እስከ ዋናው አዳራሽ በር ድረስ አይወጡም። ይህም የሆነበት ምክንያት ግርማዊነታቸው የመጡት ለሥራ ጉዳይ ስለሆነ፣ ምንም ዓይነት የኦፊሲየል አቀባበል ማዘጋጀት አስፈላጊ ስላልሆነ ነው። ይህን የመሰለውም ፕሮቶኮል ከዚህ ቀደም ለሥራ ጉዳይ ለመጡት ለብዙዎቹ ታላላቅ መሪዎች ሲደረግ የቆየ መሆኑን አስረድተውናል።

ጃንሆይ፣ ይህ የምትለን የቫቲካን የሥነ ሥርዓት ልምድ ከሆነ ማለፊያ ነው። እናንተም ይህንኑ መቀበላችሁ የተገባ ነው። ሆኖም እኛን የገረመን፣



ካርዲናል ራፋኤሌ ካርሎ ሮሲ፤ ፀረ ፋሽስትነታቸውን በግልጽ ከተናገሩት
ሊቀ ጳጳሳት አንዱ ናቸው

ለእናንተ ያልታያችሁ አንድ ነገር ነበር። ይኸውም፤ ለፕሬዚዳንት ኑሜሪ ስለተደረገው አቀባበል ነው። ቅዱስ ጳጳሱ እኛን በጽሕፈት ቤታቸው በር ላይ ተቀብለውን እውስጥ ገብተን ወንበር እንድንይዝና ንግግራችንን እንድንጀምር ሲደረግ፤ የሱዳኑ መሪ እውጭ እንዲቆዩ ተደርጐ ነበር። ከዚያም በእኛው አስተዋሽነት ወደ ጳጳሱ ቢሮ እንዲገቡ ሲፈቀድ፤ ቅዱስነታቸው የሱዳኑን መሪ የተቀበሏቸው፤ እዚያው ከወንበራቸው ላይ ሆነው ነው። ይህ ልዩነት መደረጉ ወዳጃችንን ፕሬዚዳንት ኑሜሪን የሚያስቀይማቸው አልሆነም ወይ?

ደራሲው፤ የዚህ ዓይነቱን ፕሮቶኮል በትናንትናው ቀን (ቅዳሜ ታህሣሥ 21) የጣልያን መንግሥትም አድርጐታል። የጣልያን ሬፑብሊክ ፕሬዚዳንት ሲኞር ሌዎኔ (Leone) ለግርማዊ ንጉሠ ነገሥትና ለሱዳኑ መሪ ለጄኔራል ኑሜሪ ክብር በኩሪናሌ ቤተመንግሥት ባደረጉት የምሳ ግብዣ ላይ የተከናወነው ፕሮቶኮል እንደሚከተለው ነበር።

1ኛ/ ግርማዊነትዎን ከማረፊያ ሆቴልዎ ድረስ ሄደው ከዚያ እስከ ኩሪናሌ ቤተመንግሥት ድረስ አጅበው ያመጡዎ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አልዶ ሞሮ ናቸው። ፕሬዚዳንት ኑሜሪን ግን እስከ ኩሪናሌ ይዘዋቸው የመጡት ም/የፕሮቶኮሉ ሹም ሲኞር ሞላዮኒ ናቸው።

2ኛ/ ጃንሆይ ኩሪናሌ ቤተመንግሥት ግቢ ውስጥ ሲደርሱ፤ የአንድ ሻለቃ ጦር የክብር ዘብ ተሰልፎ፤ የሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ሲኞር ሌዎኔም ከጠቅላይ ሚኒስትሩ ከሲኞር ሩሞር ጋር ሆነው ለግርማዊነትዎ ከፍተኛ የክብር አቀባበል በማድረግ ወደ ግብዣው አዳራሽ እየመሩ ወስደዎታል።

3ኛ/ ፕሬዚዳንት ኑሜሪ ግን፤ ኩሪናሌ ሲደርሱ የቤተመንግሥቱ ፕሮቶኮል ሹም ተቀብሎ ነው ወደ ግብዣው አዳራሽ የወሰዳቸው፤ ለእርሳቸው የክብር ዘብ አልተሰለፈም።

እንግዲህ ግርማዊነትዎ እንደሚመለከተው፤ በቫቲካንም ሆነ በጣልያን ቤተመንግሥት ለጃንሆይ የተደረገው አቀባበል የተለየ የሆነው እኛ አምባሳደሮችዎ ክቡር አቶ አባተ አግዴና እኔ ይህ ይደረግልን ብለን ጠይቀን አይደለም።

ጃንሆይ፤ አባተን በቫቲካን፤ አንተን በሮም እንደራሴዎቻችን እንድትሆኑ ስንመድባችሁ፤ የሁለታችሁም ኃላፊነት ለእኛና ለአገራችን መሆኑን አውቃችሁ፤ በመተባበርና በመረዳዳት እንድትሠሩ ነው እንጂ፤ ይኸ የእኔ ጉዳይ ነው ሌላው የእሱ ነው በሚል መንፈስ እንድትለያዩ አይደለም። አሁን እንደተናገርከው፤ የኛን ወደዚህ መምጣት ሁለታችሁም ተስማምታችሁ በትጋት ማዘጋጀታችሁን ምናሴ ኃይሌም ነግሮናል። ወደፊትም ይኸው የመተባበር መንፈሳችሁ እንዲቀጥል አደራችንን እንጥልባችኋለን።

ደራሲው፤ ጃንሆይ ! ክቡር አቶ አባተ አግዴ አጋጣሚ ሆኖ ዛሬ እዚህ ባይገኙም፤ ከጃንሆይ የተሰጠው መምሪያ እጅግ እንደሚያስደስታቸው እርግጠኛ ነኝ። እኔም በበኩሌ በዕድሜም በኤክስፔሪያንስም ከሚበልጡኝ ከክቡር አቶ አባተ ጋር ተባብሬ በመሥራት ብዙ ትምህርት እንደማገኝ



የካቶሊኮች አባት ቅዱስ ጳውሎስ ስድስተኛ በህዳር 9 ቀን1970 ዓ.ም በመንበረ ጴጥሮስ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን በኦፊሲየል ሲቀበሉ፣

" ... ዛሬ የግርማዊነትዎ በመካከላችን መገኘት ከፍ ያለ ግምት የሚሰጠው ጉዳይ ነው። ኢትዮጵያ ከቅድስት መንበራችን ጋር እጅግ ልዩ የሆነ ዝምድና ይዛ የኖረች አገር ነች። በመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ጉልላት ጀርባ ላይ የሚገኘው የቅዱስ እስጢፋኖስ ቤተክር ስቲያንና ገዳም ከተቆረቆረ፣ የብዙ መቶ ዓመታት ዘመን ያስቆጠረ መሆኑን ታሪክ በትክክል ይነግረናል። ስለዚህ፣ ለብዙ ዘመናት የቆየውን ታሪክ ለመጠበቅና እንዲቀጥል ለማድረግ፣ ከሌሎቹ አገሮች ሁሉ ኢትዮጵያ ብቻዋን በቫቲካን ከተማ ክልል ውስጥ የአንድ መንፈሳዊ ተቋምና የአንድ የትምህርት ኮሌጅ ባለቤት ሆና ትኖራለች። ይህንንም ይዞን ለመቆየት የቻልነው በቅዱስ አባታችን በፒዮስ 11ኛ በጐ ፈቃድና ውሳኔ መሆኑን ከጠለቀ መንፈሳዊ ስሜት ጋር እናስበዋለን ... " (ቅዱስ ጳውሎስ 6ኛ)

እርግጠኛ ነኝ። በዚህ አጋጣሚ ጃንሆይ ቢፈቅዱልኝ፤ ስለ ቫቲካን፤ እስከዛሬ ተከታትለን ያልደረስንበትን አንድ ትልቅ ጉዳይ ጃንሆይ መምሪያ ቢሰጡን በብዙ ልንጠቀምበት እንችላለን።

ጃንሆይ፤ ጉዳዩ ምንድን ነው?

ደራሲው፤ የፋሽስት ጣልያን በኢትዮጵያ ላይ ከፍተኛ ግፍ ከፈጸመ በኋላ ድል ሲሆን፤ ይቅርታ ጠይቆ የጦር ካሣም ከፍሎ ይኸው በዛሬው ሰዓት በመልካም የወዳጅነት ግንኙነት ለጋራ ጥቅማችን ተባብረን እንሠራለን። ቫቲካን ግን በአገራችን እንደሚነገረውና በአንዳንድም መጽሐፍ ላይ እንደተጠቀሰው፤ የሙሶሊኒን ዓላማ በመደገፍ ኢትዮጵያን ለመውጋት የተላኩትን በብዙ መቶ ሺህ የሚቆጠሩትን ወታደሮች፤ በዘመኑ የነበሩት ቅዱስ ፓፓው ፒዮስ 11ኛ ባርከው ቡራኬ ሰጥተዋል እየተባለ ይነገራል። ይህ እውነትነቱ እስከ ምን ድረስ እንደሆነ ባለማወቃችን፤ ከመንግሥታችንም እስከ ዛሬ ድረስ ምንም ዓይነት መምሪያ ስላልተሰጠን፤ ጋዜጠኞችና ጸሐፊዎች ለሚያቀርቡልን ልዩ ልዩ ጥያቄዎች ለመመለስ እጅግ ተቸግረናል። የጃንሆይ መልካም ፈቃድ ሆኖ በጉዳዩ ላይ አንድ ዓይነት ማብራሪያ ቢሰጠን ለሥራችን ትልቅ እርዳታ ይሆንልናል።

ጃንሆይ፤ ከመንግሥታችን ምንም ዓይነት መመሪያ ስላልተሰጠን ለሚቀርቡልን ጥያቄዎች መልስ አጥተን ተቸግረናል እያሉ ማውራት ብቻ በቂ አይደለም። በኢትዮጵያና በቫቲካን መካከል ስላለው ግንኙነት ንገሩን ብላችሁ ስትጠይቁ፤ መልሱን ማን እንደከለከላችሁ ማስረዳት አለባችሁ። እኛ እንደምናየው ስንፍናው ከእናንተም ነው። ለሥራችሁ የሚጠቅማችሁን ሁሉ መከታተልና ማጥናት የናንተ ተግባር መሆኑን ማወቅ አለባችሁ። አሁን ለጊዜው እኛ የምናስታውሰውን እንነግራችኋለን።

"... አገራችን በፋሽስት መንግሥት ስትወረር፤ በሥልጣን ላይ የነበሩት የመላው ዓለም ካቶሊኮች አባት ቅዱስ ፒዮስ 11ኛን በ1916 ዓ.ም ጣልያንን ስንጐበኝ፤ እሳቸውንም ቫቲካን ሄደን ሺዚት በማድረግ ተዋውቀናቸዋል። በዚያ ጊዜ ጳጳሱ፤ በመንበራቸው ሆነው እኛንና ተከታዮቻችንን ሲቀበሉን የገለጡልን፤ የጋለ የወዳጅነት መንፈስና ለአገራችን ለኢትዮጵያም ያላቸው አክብሮትና ፍቅር በጣም አስደስቶን እንደነበረ እናስታውሳለን። በጉብኝታችን ሰዓት በእኛ በኦርቶዶክሶችና በካቶሊኮች መካከል ክርስቲያናዊ በሆነው ዕምነታችን መልካም ግንኙነትና መረዳዳት እንዲኖር በሰፊው ተነጋግረን ግንኙነታችንን የምናካሄደው፤ ሐረር የሚገኘው የካቶሊክ ሚሲዮን ኃላፊ በሆኑትና ቀድሞ የኛ ፈረንሣዊኛ አስተማሪያችን በነበሩት በአቡነ እንድርያስ አማካይነት እንዲሆን ነበር። የጣልያን ጠቅላይ ሚኒስትር ሲኞር ሙሶሊኒ፤ የወልወልን ግጭት ሰበብ አድርጐ አገራችንን ለመውረር ጦር በሚያደራጅበት ጊዜ፤ ኢትዮጵያ ምንጊዜም ጠብ ፈላጊ አለመሆኗን ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሱ እንዲያውቁት ከነማስረጃው እያከታተልን እንጽፍላቸው ስለነበረ፤ እሳቸውም እያከታተሉ ሲመልሱልን ቆይተዋል። ሙሶሊኒ ጦርነቱን ከማንሣቱ አንድ ወር ከሚሆን ጊዜ በፊት፤ ቅዱስ ፓፓው ለመላው ዓለም የነርሶች ጉባኤ ባደረጉት ንግግር፤ <u>ግዛት ለማስፋፋት የሚደረግ ጦርነት ከሕግ ውጭ መሆኑን ደህና አድርገው መናገራቸውን</u>

እንደሰማን፣ እኛም የቅዱስነታቸውን አስተያየት በደስታ መንፈስ መቀበላችንንና፣ ምስጋናችንን አከታትለን ልከንላቸዋል። ከዚያን ቀን በኋላ የቫቲካን ድምፅ ጠፋ። በዚያን ጊዜ ፓሪስ የነበረው መላክተኛችን በላከልን ራፖር፣ ሙሶሊኒ ቅዱስ ፓፓው ለነርሶቹ ባደረጉት ንግግር ተቆጥቶ ስለዛተባቸው፣ ከእንግዲህ ወዲህ በኢትዮጵያ ነገር ምንም ዓይነት አስተያየት እንዳይሰጡ ታግደዋል ብሎ ነገረን። እኛ ግን ቅሬታ አድሮብን የነበረው፣ ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ይገድለሁ ካለ በኋላ፣ በሕዝባችን ላይ ያንን ሁሉ ግፍ ሲፈጽም፣ ከመንበረ ጴጥሮስ ቤተክርስቲያን ምንም ዓይነት አስተያየት ሳይሰጥ በመቅረቱ ነበር። ይኸውም፣

- በግራዚያኒ ላይ ቦንብ ተጣለ በማለት ለሦስት ቀናት ሳያቋርጥ የአዲስ አበባን ሕዝብ በመሣሪያ ብቻ ሳይሆን ቤቱን በማቃጠል፣ በአካፋና በዶማ ሰውነቱን በመፍለጥ ያንን ሁሉ ጭካኔ ሲፈጽም፣

- የታወቁት የኦርቶዶክስ ኃይማኖታችን መሪዎች አቡነ ጴጥሮስና አቡነ ሚካኤል፣ የኢትዮጵያ ሕዝብ ለነፃነቱ ትግሉን እንዲቀጥል ሰብካችኋል በመባል በመትረየስ ሲደበደቡ፣

- በደብረ ሊባኖስ ገዳም ያሉት ቁጥራቸው ከአራት መቶ በላይ የሆኑት መነኰሳትና መናኒያን እንደዚያ በሚያሰቅቅ ሁኔታ ሲጨፈጨፉ፣

ይህ ሁሉ ግፍ ከክርስትና ዕምነት፣ ከሰብአዊ መንፈስና ከሥልጣኔ ውጭ የተፈጸመ መሆኑን ቅዱስ ፓፓው እየሰሙ እንዴት ዝም አሉ? ብለን እኛም ቅሬታ ተሰምቶን ነበር። ኋላ ግን በአውሮፓ ያሉት አንዳንድ ወዳጆቻችን እንደነገሩን፣ በዚያን ዘመን ጳጳሱ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ የሚፈጽመውን ግፍ በማውገዝ አንድ መግለጫ ቢሰጡ፣ የሚያስከትልባቸውን አደጋ በማሰብ ዝምታን መምረጣቸውን ሰምተናል። ከዚህ ሌላ፣ ጳጳሱ ከሙሶሊኒ ጋር በሐሳብ መስማማታቸውና ወደ ኢትዮጵያ የተላኩትንም የፋሽስት ወታደሮች ከነመሣሪያዎቻቸው ባርከው አሰናብተዋል ተብሎ የተወራውን የሚያረጋግጥ መረጃ አላገኘንም። በእኛ አስተያየት ይህ የተወራው እውነት ቢሆን ኖሮ፣ ሙሶሊኒ ለፕሮፓጋንዳው ጥቅም ሲል በፎቶግራፍና በሲኒማም አትልቶ በዓለም ላይ እንዲታይ ያደርግ እንደነበረ የታወቀ ነው። እርግጥ ነው! አንዳንዶቹ ጳጳሳት በየግላቸው የፋሽስት መንግሥት ደጋፊ በመሆን ንግግር ማድረጋቸውንና ያላቸውንም የጌጣጌጦች ሀብት እርዳታ እያሉ ለሙሶሊኒ ማቅረባቸው በይፋ ታይቷል። ይሁን እንጂ፣ በዚህ ሁሉ ጉዳይ ጳጳሱ ያልተስማሙበትና ያልተባበሩበት መሆኑን ቫቲካንን በጠቅላይ ሚኒስትር ደረጃ የሚመሩትና ኋላ ፒዮስ ፲፪ኛ ተብለው የተመረጡት ሊቀጳጳስ፣ ፓሪስ ለሚገኘው ሚኒስትራችን ለብላቴን ጌታ ወልደማርያም በጽሑፍ አረጋግጠውለታል። አሁን ይህ ታሪክ ካለፈ ከበዙ ዘመናት በኋላ ወደ ኋላ ተመልሰን እንደገና ማብጠርና መከታተል ምንም አይጠቅመንም። እኛና መንግሥታችን ጠላታችን ሆኖ ብዙ ጥቃት ካደረሰብንም አገር ከጣልያን ጋር ታርቀን ይኸው አሁን ለጋራ ጥቅማችን እንሥራ! እየተባባልን ወዳጅነት ዘርግተናል። ከቫቲካንም ጋር ከመሠረት የተጀመረውን መልካም ግንኙነት መቀጠል እንጂ፣ ሌላ ታሪክ መፈለግና መመራመር አያስፈልግም። ዛሬ በአለንበት ዓለም፣ ክርስቲያኖች የሆንን ሕዝቦች ሁሉ ዕምነታችንንና አንድነታችንን በማጠንከር፣ ለጋራው ጥቅማችን በርትተን በመሥራት ፋንታ፣ እርስ በርሳችን የሚለያየንን እና የሚያጣላንን ፈለግ ለማግኘት የምናደርገው ጥረት የሚጐዳን እንጂ፣ የሚበጀን አለመሆኑን በቶሎ ብንገነዘበው

ይሻላል ... " በሚል መሪ ቃል፤ እኔ በማስታወሻዬ የመዘገብኩት የጃንሆይ ማብራሪያ እዚህ ላይ ተፈጸመ።

እንግዲህ ከዚህ በላይ ተዘርዝሮ እንደቀረበው፤ የመንበረ ጴጥሮስ ካቶሊካዊት ቤተክርስቲያን መሪ ቅዱስ ፒዮስ ፲፩ኛ ከዲክታተሩ ፋሽስት ከቤኒቶ ሙሶሊኒ ጋር ተባብረው ለኢትዮጵያ ነፃነት መገፈፍ ረድተዋል የተባለው ወሬ ከመሠረቱ የራቀና ማስረጃ ያልተገኘለት መሆኑን በበለጠ መገንዘብ ይቻላል። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እንደተናገሩትም፤ ቅዱስ ፓፓው የመላው ዓለም ካቶሊኮች መንፈሳዊ አባት እንደመሆናቸው መጠን፤ የፋሽስት መንግሥት በክርስቲያኑ በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ ያንን ሁሉ ግፍ ሲያደርስና የአረመኔ ተግባር ሲፈጽም፤ አደባባይ ወጥተው በማውገዝ ፋንታ ዝምታን የመረጡት፤ ሙሶሊኒ የሚያደርስባቸውን አደጋ ለመከላከል የሚያስችል አቅም ስለሌላቸው መሆኑ ግልጽ ነው። ከታሪኩ ሂደት እንደምንረዳው፤ ፓፓው በኢትዮጵያ ላይ ጦርነት እንዳይካሄድ የተቻላቸውን ሁሉ ለማድረግ ሞክረዋል። ለምሳሌም ያህል፤ አሁን በመጨረሻ በቫቲካን የተገኘው ሰነድ እንደሚያሳየው፤ ፒዮስ ፲፩ኛ ጦርነቱ ከመጀመሩ ጥቂት ቀናት በፊት፤ ለሙሶሊኒ አንድ ልዩ ደብዳቤ በብዕራቸው ጽፈው ለመላክ ረቂቁን አዘጋጅተው ነበር። በዚህ ደብዳቤያቸው የፋሽስቱን መሪ ለመለመን የፈለጉት፤ " ... ጣልያንን የሚያህል የክርስቲያን መንበር፤ የሥልጣኔ ምንጭና የታሪክ አገር፤ እንዴት በጦር ኃይል በሌላው ነፃ መንግሥት ላይ የሕገወጥና የግፍ ሥራ ትፈጽማለች ተብላ በመላው ዓለም ትወገዛለች? ... " በሚል መንፈስ ዲክታተሩ እንዲራራ ለማድረግ ነበር። ነገር ግን የፖፑ አማካሪዎች ሁሉ ተሰብስበው ከተነጋገሩበት በኋላ፤ " ... ሙሶሊኒ ይህ ደብዳቤ ቢደርሰው፤ በቁም ነገር አይቀበለውም። መሠረተ ሐሳቡንም በምንም ምክንያት አይለውጥም። ቀጥሎ ደግሞ መንበረ ቅድስት ቤተክርስቲያናችን ዐርፋ አልተቀመጠችም በማለት ሌላ ተንኮል ሊያቅድብን ይችላል ... " የሚል አስተያየት ስለሰጡ፤ የተረቀቀው ደብዳቤ ለፋሽስቱ መሪ ሳይላክለት ቀርቷል። ይህም ረቂቅ ደብዳቤ ዛሬ በቫቲካን ምሥጢራዊ ዶክመንቶች ውስጥ በፒዮስ ፲፩ኛ ፋይል ውስጥ ተያይዞ ይገኛል።

እንግዲህ! ማንም ሰው የቀረበውን ታሪክ በዝርዝር ተመልክቶ እንደሚረዳው፤ የመንበረ ቅዱስ ጴጥሮስ ቤተክርስቲያን መሪ ፒዮስ ፲፩ኛ፤ ኢትዮጵያ በፋሽስት መንግሥት በተጠቃችበት ዘመን፤ የሙሶሊኒ ተባባሪ እንዳልነበሩ ሊገነዘብ ይችላል። ይልቁንም ቅዱስ ፓፓው ለኢትዮጵያ አዛኝና የተለየ አስተያየት የነበራቸው መንፈሳዊ አባት እንደሆኑ የቀረቡት ማስረጃዎች በቂዎች ናቸው። የሚያሳዝነው፤ ፒዮስ ፲፩ኛ የኢትዮጵያ ነፃነት ከፋሽስት ከመላቀቁ ከሁለት ዓመታት በፊት 1939 ዓ.ም ከዚህ ዓለም በሞት መለየታቸው ነው። " ... በአንድ ትልቅ ነጭ ባሕር ውስጥ አንድ የጥቁር ምልክት ውበት አላት ..." ብለው በ1931 ዓ.ም የተናገሩትን ቃል ዛሬ በቫቲካን ቅጥር ግቢ ውስጥ የሚገኘው የኢትዮጵያ ኮሌጅ ሻማ እያበራ በፀሎት ያስታውሳታል።



ቅዱስ ዮሐንስ ጳውሎስ ዳግማዊ፤ ደራሲውን በመንበረ ጴጥሮስ
ተቀብለው ሲያነጋግሩ፤